፴፯ ፤ ውእቱ ፡ የአምር ፡ ዘእንበለ ፡ ይትፈጠር ፡ ዓለም ፡ ምንት፡ ውእቱ፡ ዓለም ፤

ዓለም ፡ ሳይፈጠር ፡ ይህ ፡ ዓለም ፡ ምን ፡ እንደሆነ ፡ እርሱ ፡ ያውቃል ፤

ወለትውልደ ፡ ትውልድ ፡ ዘይከውን ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ዘመን ፡ የሚሆ ነውን ፡ ነገር ፡ ያውቃል ፤

፴፰ ፤ ይባርኩከ ፡ እለ ፡ ኢይነውሙ ፡ ወይቀውሙ ፡ በቅድመ፡ ስብሐቲከ ፤

የማያርፉ ፣ በጌትነትህም ፡ ፊት፡ የሚቆሙ ፡ መላእክት ፡ ያመሰ ግኑሃል፤

፴፱ ፤ ወይባርኩ ፡ ወይሴብሑ ፡ ወያሌዕሉ ፡ እንዘ ፡ ይብሉ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ፡ ቅዱስ፡ እግዚእ ፡ መናፍስት ፤

የመላእክት ፡ ጌታ ፡ ንጹሕ ፣ ክቡር ፡ ልዩ ፡ አንተ ፡ ነህ ፡ እያሉ ፡ ፈጽመው ፡ ያመሰግናሉ፡ ከፍ ፡ ከፍም ፡ ያደርጋሉ ። ቅዱስ ፣ ቅዱስ ፣ ቅዱስ ፡ ብሎ ሦስትነቱን ፣ እግዚእ ፡ መናፍ ስት ፡ ብሎ ፡ አንድነቱን ፡ ተናገረ ፤ አንድም ፡ ቅዱስ ፡ ብሎ ፡ ፩ነቱን ፡ ተናገረ ፤ ሰ፫ቱ ፡ ሁሉ ፡ ልብ ፡ ቃል ፡ እስትንፋስ ፡ ቢኖራቸው ፡ ቅዱሳን፡ቅዱሳን ፡ ባለ ፡ ነበርና፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ብሎ፡ ፫ት ፡ ጊዜ ፡ መናገሩ ፡ የ፫ነቱ ፡ ነው ፤

ወይመልእ ፡ ምድረ ፡ መናፍስት ፤

ፍጥረታት ፡ ያሉባትን ፡ ምድር በምልዓት ፡ ይመላል ፤ አንድም፡ ምድረ ፡ መናፍስተ ፡ ቢል ፡ ፍጥረታትን ፡ በምድር ፡ ይመ ላል፤ አንድም ፡ ምስጋናን ፡ በምድር ፡ ይመላል ፤

፵ ፤ ወበህየ ፡ ርእያ ፡ አዕይንትየ ፡ ኵሎ ፡ እለ ፡ ኢይነውሙ ፡ ይቀውሙ ፡ ቅድሜሁ ፡ ወይባርኩ ፤

በዚያም ፡ ቦታ ፡ የማያርፉ ፡ መላእክትን ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ቁመው ፡ ሲያመሰግኑ ፡ ዓይኖቼ ፡ አዩ ፤

፵፩ ፤ ወይብሉ ፡ ቡሩክ ፡ አንተ ፡ ወቡሩክ ፡ ስሙ ፡ ለእግዚእ ፡ መናፍስት ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤

አንተ ፡ የከበርክ ፡ ነህ ፤ የመላ እክት ፡ ጌታ ፡ ስሙም ፡ ለዘለ ዓለም ፡ የከበረ ፡ ነው ፡ ይላሉ ፤

፵፪ ፤ ወተወለጠ ፡ ገጽየ ፡ እስከ ፡ ስእንኩ ፡ ነጽሮ ፤

ቀና ፡ ብሎ ፡ ማየት ፡ እስኪሳ ነኝ ፡ ድረስ ፡ ዓይነ ፡ ልቡናዬ ፡ ተለወጠ ።

## ምዕራፍ ፲

፩ ፤ ወርኢኩ ፡ እምድኅረዝ ፡ አእ ላፈ አእላፋት ፡ ወትእልፊተ ፡ አእላ ፋት፤

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ፈጽመው ፡ የበዙ ፡ የብዙ ፡ ብዙ ፡ የሚሆኑ መላእክትን ፡ አየሁ ፤

ወእልቦሙ ፡ ኍልቍ ፡ ወሐሳብ ፡ ለእለ ፡ ይቀውሙ ፡ ቅድመ ፡ እግዚእ መናፍስት፤

ኍልቍና : ወሐሳብ : አንድ : ወገን : ነው ፤ ቍጥር : የላቸውም ፤ አንድም : ለየራሱ : ለማውጣት : ቍጥር : የላቸውም ፤ ወሐሳብ ፤ ግምገማ : የላቸውም ፤

፪ ፤ ወርኢኩ : በ፬ቱ : ክነፊሁ : ለእግዚአ : መናፍስት : ፬ተ : ገጻተ : ካልዓተ : እምእለ : ይቀውሙ ፤

በእግዚአ : መናፍስት : አጠገብ ባራቱ : መዓዝን : ከሚቆሙት : የተለዩ : ሌሎች : አራቱን : መላእክት : አየሁ ፤

፫ ፤ ወአስማቲሆሙ : አአመርኩ : ዘአይድዐኒ : አስማቲሆሙ : መልአክ : ዘመጽአ : ምስሌየ ፤

ስማቸውንም : አወቅሁ ፤ ስማቸውንም : የነገረኝ : ከእኔ : ጋራ የመጣ : መልአክ : ነው ፤

፬ ፤ ወኵሎ : ኅቡዓተ : አርአየኒ ፤ የተሰወረውንም : ሁሉ : ገለጠልኝ ፤

ወሰማዕኩ : ቃሎሙ : ለእልክቱ : ፬ቱ : ገጽ : እንዘ : ይሴብሑ : ቅድመ : እግዚአ : ስብሐት ፤

በክብር : ባለቤት : ጌታም : ፊት : ሲያመሰግኑ : የነዚያን : የአራቱን : መላእክት : ቃል : ሰማሁ ፤

፭ ፤ ወቃል : ቀዳማዊ : ይባርኮ : ለእግዚአ : መናፍስት : ለዓለመ : ዓለም ፤

መጀመሪያውም : ቃል : የመላእክት : ጌታን : ለዘለዓለሙ : ያመሰግነዋል ፤ ቅዱስ : ሚካኤል : ነው ፤

፮ ፤ ወቃለ : ካልዓ : ሰማዕኩ : እንዘ : ይባርኮ : ለኅሩይ ፤

ቅዱስ : ሩፋኤል : ኅሩይ : ክርስቶስን : ሲያመሰግነው ፤

ወለኅሩያን : እለ : ስቁላን : ለእግዚአ : መናፍስት ፤

ለርሱ : ብለው : እርሱን : ወደው : የሠሩት : ሥራ : ጸንቶ : የሚኖርላቸው ፤ አንድም : ለእነርሱ : ብሎ : እነርሱን : ወዶ : የሠራላቸው : ሥራ : ጸንቶላቸው : የሚኖር : ኅሩያን : ጻድቃንን : ሲያመሰግን : ሰማሁ ፤

፯ ፤ ወሣልሰ : ቃለ : ሰማዕኩ : እንዘ : ይስእሉ : ወይጼልዩ : በእንተ : እለ : የኀድሩ : ውስተ : የብስ ፤

ዲበ : የብስ : ሲል : ነው ፤ በዚህ : ዓለም ፤ ስለሚኖሩ : ሰዎች ፤

ወያስተበቍዑ : በስሙ : ለእግዚአ : መናፍስት ፤

በመላእክት : ጌታ : ስምም : እምነው : ስለሚለምኑ : ሰዎች : ፈጽመው : ሲለምኑ : ሦስተኛውን : ቃል : ሰማሁ : (ገብርኤል : ነው)

፰ ፤ ወቃለ : ራብዓየ : ሰማዕኩ : እንዘ : ይሰድዶሙ : ለሰይጣናት ፤

ሰይጣናትን : እያስወጣ : ሲሰዳቸው : አራተኛውንም : ቃል : ሰማሁ ፤ (ፋኑኤል : ነው :)

፱ ፤ ወኢየኀድጎሙ : ይባኡ : ኀበ : እግዚአ : መናፍስት : ከመ : ያስተዋድይዎሙ : ለእለ : የኀድሩ : ውስተ : የብስ ፤

በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎ
ችን ፡ ያጣሏቸው ፡ ዘንድ ፡ ወደ
መላእክት ፡ ጌታ ፡ እንዲገቡ ፡
አይተዋቸውም ፤

፲ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ ተስእልክዎ ፡
ለመልአክ ፡ ሰላም ፡ ዘየሐውር፡ ምስ
ሌየ ፡ ዘውእቱ ፡ አርአየኒ ፡ ኵሎ ፡
ዘኅቡእ ፤

ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከእኔ ፡ ጋራ ፡
የሚኖር ፡ ፍቅር ፡ አንድነት ፡
ያለው ፡ መልአኩን፡ ጠየቅሁት
የተሰወረውንም ፡ ሁሉ ፡ የገለጠ
ልኝ ፡ እርሱ ፡ ነው ፤

፲፩ ፤ ወእብሎ ፡ መኑ ፡ ውእቶሙ ፡
እሉ ፡ አርባዕቱ ፡ ገጽ ፡ ዘርኢኩ ፡
ወእለ ፡ ሰማዕኩ ፡ ቃሎሙ፡ ወጸሐፍ
ክዎሙ ፤

ያየኋቸው ፤ ቃላቸውንም ፡ የሰ
ማሁት ፡ እሊህ ፡ አራቱ ፡ መላ
እክትን ፡ ቈጠርኋቸው ፤ እነ ፡
ማናቸው ? ብዬ ፡ ፋኑኤልን ፡
ጠየቅሁት፤ ፋኑኤል ፡ ማለት ፡
ማኅፈደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ማለት ፡
ነው ፤

፲፪ ፤ ወይቤለኒ ፡ ዝ ፡ ቃል ፡ ቀዳ
ማዊ ፡ ውእቱ ፡ መሐሪ ፡ ወርኁቀ ፡
መዓት ፡ ቅዱስ ሚካኤል ፤

እርሱም ፡ መጀመሪያው ፡ ቃል፡
ይቅር ፡ የሚል ፡ ከመዓትም ፡
የራቀ ፤ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡
ነው ፡ አለኝ፤

፲፫ ፤ ወካልዕ ፡ ዘዲበ ፡ ኵሉ፡
ሕማም ፤

ሁለተኛውም ፡ በበሽታው ፡ ሁሉ
ላይ ፤

ወዲበ ፡ ኵሉ ፡ ቍስል ፡ ዘውሉደ ፡
ሰብእ ፡ ውእቱ ፡ ሩፋኤል ፤

በሰው ፡ ልጆችም ፡ ቍስል ፡
ሁሉ ፡ ላይ ፡ የተሾመ ፡ ቅዱስ
ሩፋኤል ፡ ነው ፡ አለኝ ፤

፲፬ ፤ ወሣልስ ፡ ዘዲበ ፡ ኵሉ ፡
ኃይል ፡ ውእቱ ፡ ቅዱስ ፡ ገብርኤል ፤

ሦስተኛውም ፡ በመላእክት ፡ ሁሉ፡
ላይ ፡ የተሾመ ፡ ቅዱስ ፡ ገብርኤል ፡
ነው ፡ አለኝ ፤

፲፭ ፤ ወራብዕ ፡ ዘዲበ ፡ ንስሓ ፡
ለተስፋ ፡ እለ ፡ ይወርሱ ፡ ሕይወተ ፡
ዘለዓለም ፡ ውእቱ ፡ ፋኑኤል ፤

አራተኛውም ፡ የዘለዓለም ፡ ሕይ
ወትን ፡ ለሚወርሱ ፡ ሰዎች ፡
ተስፋ ፡ ሲሆን ፡ ንስሐ ፡ በሚ
ገቡ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ የተሾመ ፡
ፋኑኤል ፡ ነው ፡ አለኝ፤

፲፮ ፤ ወእሉ ፡ ፬ቱ ፡ መላእክቲሁ ፡
ለእግዚአብሔር ፡ ልዑል፤

ከፍ ፡ ያለ ፡ የእግዚአብሔር ፡
አራቱ ፡ መልእክተኞች ፡ እሊህ
ናቸው ፤ አንድም ፡ አሁን ፡ አስ
ቀድሞ ፡ የተናገራቸው ፤ አንድም፡
አራቱ ፡ ኪሩቤል ፡ ናቸው ፤

ወ፬ተ ፡ ቃለ ፡ ሰማዕኩ ፡ በውእቱ ፡
መዋዕል ፤

በዚያም ፡ ወራት ፡ አራቱን ፡
ቃሎች ፡ ሰማሁ ፡ አለ ፡፡

## ምዕራፍ ፲፩

፩ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ ርኢኩ ፡ ኵሎ፡ ኅቡዓቲሆሙ ፡ ለሰማያት ፤
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በሰማይ ፡ የተሰወሩ ፡ ምሥጢሮችን ፡ ሁሉ ፡ አየሁ፤

፪ ፤ ወመንግሥት ፡ እፎ ፡ ትትከፈል ፤
መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ተመጥኖ ፡ ተመጥኖ ፡ እንዲሰጥ ፡ አየሁ ፤
ወተግባረ ፡ ሰብእ ፡ ከመ ፡ በመዳልው ይዴለው፤
የሰው ፡ ምግባሩ ፤ ትሩፋቱ ፡ እንዲመዘን ፤ የትሩፋቱ ፡ ዋጋ ፡ ተመጥኖ ፡ እንዲሰጥ ፡ አየሁ፤

፫ ፤ ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ ማኅደርሙ ፡ ለኅሩያን ፤ ወማኅደሮሙ ፡ ለጻድቃን ፤
በዚያም ፡ ቦታ ፡ የተመረጡ ፡ የጻድቃን ፡ ማደሪያ ፤ መንግሥተ ፡ ሰማይን ፡ አየሁ ፤

፬ ፤ ወርእያ ፡ አዕይንትየ ፡ በህየ ፡ ኵሎሙ ኃጥአን ፡ እንዘ ፡ ይሰደዱ ፡ እምህየ ፡ እለ ፡ ይክህድዎ ፡ ለስመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤
የመላእክት ፡ ጌታን ፡ ስም ፡ የካዱ ፡ ኃጥአንም ፡ ሁሉ ፡ ከመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ወጥተው ፡ ሲሰደዱ ፡ ዓይኖቼ ፡ አዩ ፤

፭ ፤ ወይስሕብዎሙ ፤
መላእክት ፡ ስበው ፡ ያወጧቸዋል ፤
ወቀዊም ፡ አልቦሙ ፡ በመቅሠፍት ፡ እንተ ፡ ትወፅእ ፡ እምእግዚአ ፡ መናፍስት ፤
ከመላእክት ፡ ጌታ ፡ በምትወጣ ፡ መቅሰፍት ፡ በመከራው ፡ መጽናት፡ አይቻላቸውም፤

፮ ፤ ወበህየ ፡ ርእያ ፡ አዕይንትየ ፡ ኅቡኣተ ፡ መባርቅት ፡ ወነጕድጓድ ፤
ከዚያም ፡ ቦታ ፡ የነጐድጓድ ፤ የመባርቅት ፡ ምሥጢርን ፡ አየሁ ፤
ወኅቡኣተ ፡ ነፋሳት፤
የነፋሳትንም ፡ ቦታ ፡ አየሁ ፤
ወእፎ ፡ ይትከፈሉ ፡ ከመ ፡ ይንፍሑ ዲበ ፡ ምድር፤
በዚህም ፡ ዓለም ፡ ነፋሳት ፡ ተመጥነው ፡ ተመጥነው ፡ እንዲወጡ ፡ አየሁ ፤
ኅቡኣተ ፡ ደመና ፡ ወጠል ፤
የጠልና ፡ የደመናትን ፡ ምሥጢር ፡ አየሁ ፤

፯ ፤ ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ እምኀበ፡ ይወፅኡ ፡ በውእቱ ፡ መካን ፤
በዚያም ፡ ቦታ ፡ የሚወጡበትን ፡ አየሁ ፤
ወእምህየ ፡ ይጸግቡ ፡ ጸበለ ፡ ምድር፤
ይጸግቡም ፡ ካለ ፡ ፀበላት ፤ ጸበልም ፡ ካለ ፡ ይፀግብ ፡ ቢል ፡ በቀና ፡ ነበር ፤ ልማደ ፡ መጽሐፍ ፡ ነው ፤ ከደመናውም ፡ የምድር ፡ ትቢያዎች ፡ ዝናሙን ይጠግባሉ፤

፰ ፤ ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ መዛግብተ ፡ ዕጽዋነ ፤
የተዘጉ ፡ ጎዋጎውን ፡ (ደጃፎችን) አየሁ ፤
ወእምኔሆሙ ፡ ይትከፈሉ ፡ ነፋሳት ፤
ከነዚያም ፡ ነፋሳት ፡ እየተመጠኑ ፡ ይወጣሉ፤
፱ ፤ ወመዝገበ ፡ በረድ ፤ ወመዝገበ ፡ ጊሜ ፤ ወዘደመናት ፤
የነፋስ ፤ የጉም ፤ የበረድን ፤ ቦታ ፡ አየሁ ፤
ወደመና ፡ ዚአሁ ፡ እምላዕለ ፡ ምድር፡ የነድር ፡ እምቅድመ ፡ ዓለም፤
ዚአሁ ፡ ለበረድ ፤ ለዝናም ፤ ለጠል ፤ ነው ፤ ደመናው ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ በምድር ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፤
፲ ፤ ወርኢኩ ፡ መዛግብተ ፡ ፀሐይ ፡ ወወርኅ ፡ ወእምአይቴ ፡ ይወፅኡ ፡ ወአይቴ ፡ ይገብኡ ፤
ከየትም ፡ እንደሚወጡ ፡ ወዴትም ፡ እንደሚገቡ ፡ የጨረቃንና ፡ የፀሐይን ቦታ ፡ አየሁ ፤
ወግብአቶሙ ፡ ስቡሕ ፤
የፀሐይ ፡ የጨረቃ ፡ መመለሻቸው ፡ ብርሃን ፡ ነው ፤
፲፩ ፤ ወእፎ ፡ ይከብር ፡ ፩ዱ ፡ እምካልኡ ፡ ወምሕዋርሙ ፡ ብዑል፤
ከጨረቃ ፡ ፀሐይ፤ ከከዋክብት ፡ ጨረቃ ፡ እንድትበልጥ ፡ አየሁ፤
አካሔዳቸውም ፡ በብርሃን ፡ የከበረ ፡ ነው ፤
ወኢየኅልፉ ፡ ምሕዋረ ፤
እምሕዋሮሙ ፡ ሲል ፡ ነው፤
ፀሐይ ፡ በመዓልት፤ ጨረቃ ፡ በሌሊት ፡ ከመውጣት ፡ አይከለከሉም ፤
ወኢይዌስኩ ፡ ወኢያሐፅፁ ፡ ምሕዋረ ፡ ዚአሆሙ ፤
ፀሐይ ፡ ከ፫፻፷፭ ፤ ጨረቃ ፤ ከ፫፻፶፬ ፤ ቀን ፡ በላይ ፡ አያተርፉም ፤ አይጨምሩም ፤ ወኢየሐፅፁ ፡ ከ፫፻፷፭ ፤ ከ፫፻፶፬ ቀን አያንሱም ፤ አይጨምሩም ፤
ሐተታ ፡ ፀሐይ ፡ ከዓመት ፡ እስከ ፡ ዓመት ፡ አሥራ ፡ ሁለት ፡ ወር ፡ ሲመላለስ ፤ ሲወጣ ፡ ሲገባ ፡ ይኖራል ፤ ሕፀፅ ፡ የለውም ፤ ከቀኑ ፡ አይጐድልም ፤ ቀንንም ፡ አያጐድልም ፤ ጨረቃ ፡ ግን ፡ ከዓመቱ ፡ ከአሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ወር ፡ አንድ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ትጐድላለች ፤ ጠፍነቷ ፡ ከአንዱ ፡ ወር ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ነው ፤ ከአንዱ ፡ ወር ፡ አንድ ፡ ቀን ፤ ከአንዱ ወር ፡ አንድ ፡ ቀን ፤ ነው ፤ በነጋታው ፡ ትወጣለች ፤ ፀሐይን ፡ አትከተልም ፤ ትውላለች ፤ ስትገባ ፡ ብርሃኗን ፡ አቃላባት ፡ ነው ፤ ያንጊዜም ፡ ጨረቃ ፡ ስትፈጠር ፡ ተፈጥራ በነጋታው ፡ ስትወጣ ፤ ከጻድቃንና ፡ ከእንስሳት ፡ በቀር ፤ ያልበቃ ፡ ሰው ፡ አያያትም ፤ እነርሱ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ጥሬ ፡ ቀጥና ፡ ያይዋታል ፤

፲፪ ፤ ወሃይማኖቶሙ ፡ የዐቅቡ ፡ አሐዱ ፡ ምስለ ፡ ካልኡ ፤
ጸንተው ፡ በኖሩባትም ፡ ሥር ዓት ፡ አንዱ ፡ ካንዱ ፡ ጋራ ፡ ሥራቸውን ፡ (ሃይማኖታቸውን) ይጠብቃሉ ፤
በመሐላ ፡ ዘነበሩ ፤
ዘነደሩ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ በመ ሐላ ፡ የጸኑበትን ፡ የተማማለ ፡ ጸንቶ ፡ እንዲኖር ፡ ጸንተው ፡ ይኖራሉ ፤

፲፫ ፤ ወይወፅእ፡ቅድመ፡ፀሐይ፤
ፀሐይ ፡ ከሁሉ ፡ አስቀድሞ ፡ ይወጣል ፤
ወይገብር ፡ ፍኖቶ ፡ በትእዛዘ ፡ እግዚእ ፡ መናፍስት ፤
በነፋሳት ፡ ጌታ ፡ ትእዛዝም ፡ ጎዳናውን ፡ ያደርጋል ፡ (ይፈ ጽማል)፤
ወይጸንዕ፡ ስሙ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤
የፀሐይ ፡ ብርሃኑ ፤ የእግዚአብ ሔር ፡ ስሙ ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፤

፲፬ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ ርኢኩ ፡ ፍኖተ ዘኅቡእ ፡ ወዘክሡት ፡ ዘወርኅ፤
ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የጨረቃን ፡ የሕፀፁን ፡ የምልዓቱን ፤ አንድም ፡ የጠፋን ፡ የሠርቁን ፡ አየሁ፤
ወምሕዋረ ፡ ፍኖቱ ፡ ይፌጽም ፡ በውእቱ ፡ መካን ፡ በመዓልት ፡ ወበሌሊት ፤
የጉዳናውንም ፡ መሄጃ ፡ በዚያ ቦታ ፡ በሌሊትና ፡ በቀን ፡ ይጨር ሳል ፤

፲፭ ፤ ወ፩ዱ፡ለካልኡ፡ይኔጽር፤
በምልዓት ፡ ጊዜ ፡ ፀሐይ ፡ ሲገባ ፤ ጨረቃ ፡ ሲወጣ ፤ አንድም ፡ ጨረቃ ፡ ሲገባ ፤ ፀሐይ ፡ ሲወጣ ፡ ያየዋል ፤
በቅድመ ፡ እግዚእ ፡ መናፍስት ፤
በመናፍስት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፤ አንዱ ፡ ሁለተኛውን ፡ ያየዋል ፡ ጨረቃና ፡ ፀሐይ ፤

፲፮ ፤ ወየአኩቱ ፡ ወይሴብሑ ፡ ወኢየአርፉ ፡ እስመ ፡ አኰቴቶሙ ፡ ዕረፍቶሙ ፡ ውእቱ ፡ ሎሙ ፤
ፈጽመው ፡ ያመሰግናሉ ፤ ለእ ነርሱ ፡ ምስጋናቸው ፡ ዕረፍታ ቸው ፡ ነውና ፤ አንድም ፡ ዕረፍ ታቸው ፡ ምስጋናቸው ፡ ነውና ፤
እስመ ፡ ፀሐይ ፡ ብሩህ ፡ ብዙኅ ፡ ሙያጤ ፡ ቦቱ ፤
ቦቱ ፡ ለፀሐይ ፡ ሲል ፡ ነው ፤
ብሩህ ፡ ፀሐይ ፡ መለወጥ ፡ አለበትና፤
ለበረከት ፡ ወለመርገም ፤
ቢጸና፡ ለመርገም፤ ባይጸና ፡ ለበ ረከት ፤ አንድም ፡ ቢያመልኩት ለመርገም ፤ ባያመልኩት ፡ ለበረ ከት፤ አንድም ፡ ሲሰርቁ ፡ ሲቀሙ ፤ ቢውሉበት ፡ ለመር ገም፤ ቢጾሙበት ፤ ቢጸልዩበት ፡ ለበረከት ፡ ይሆናል ፤

፲፯፤ ወምርዋጸ ፡ ፍኖቱ ፡ ለወርኅ ፤
የጨረቃ ፡ የመንገዱ ፡ አካሔድ፤
ለጻድቃን ፡ ብርሃን፤
በስሙ ፡ ላመኑ ፡ ጻድቃን ፡ ብርሃን ፡ ነው ፤

ወለኃጥአን ፡ ጽልመት ፤
ስሙን ፡ ለካዱ ፡ ለኃጥአን ፤
ግን ፡ ጨለማ ፡ ነው ፤
በስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፤
በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስም ፡ ላላ
መኑ ፡ ኃጥአን ፡ ግን ፤ ጨለማ
ነው ፡ አለ ፤ ቢያመልኩት ፡ ጽል
መት ፤ ባያመልኩት ፡ ብርሃን ፤
አንድም ፡ ቢሰርቁበት ፡ ቢቀ
ሙበት ፡ ጽልመት ፤ ቢጸሙበት
ቢጸልዩበት ፡ ብርሃን ፤ አንድም
ቢቈጥሩበት ፡ ጽልመት ፤ ባይቈ
ጥሩበት ፡ ብርሃን ፡ ነው ፤
ዘፈጠረ ፡ ማዕከለ ፡ ብርሃን ፡ ወማ
ዕከለ ፡ ጽልመት ፤
በጨለማና ፡ በብርሃን ፡ መካከል
ድንበር ፡ ተለየ ፤
፲፰ ፤ ወከፈለ ፡ መንፈሰ ፡ ለሰብእ ፤
ለሰው ፡ ዕውቀትን ፡ ለይቶ ፡
ለይቶ ፡ ያደለ ፤
ወአጽንዐ ፡ መንፈሰሙ ፡ ለጻድቃን ፡
በስመ ፡ ጽድቀ ፡ ዚአሁ ፤
በቸርነቱ ፡ ስም ፡ ያመኑ ፡ የጻ
ድቃንን ፡ ልቡናቸውን ፡ በእውነ
ተኛ ፡ ስሙ ፡ ያጸና ፤
፲፱ ፤ እስመ ፡ መልአክ ፡ ኢይክልእ ፤
ልስጥ ፡ ቢል ፡ አለቃ ፡ አይከ
ለክልምና ፤
ወሥልጣን ፡ ኢይክል ፡ ከሊዐ ፤
ሥልጣን ፡ ያለው ፡ ንጉሥ ፡
መከልከል ፡ አይቻለውምና ፤ አን
ድም ፡ መልአክ ፡ ቢል ፡ በቁሙ
መልአክ ፡ ነው ፤ ወሥልጣን ፡
ሰው ፡ መከልከል ፡ አይቻለው
ምና ፤
እስመ ፡ መኰንን ፡ ለኵሎሙ ፡
ይሬኢ ፤
ፈታሒ ፡ በጽድቅ ፡ ስለሆነ ፤
ወእሉንተ ፡ ኵሎሙ ፡ በቅድሜሁ ፡
ውእቱ ፡ ይኴንን ፤
እነዚህን ፡ ሁሉ ፡ እርሱ ፡ በፈ
ቃዱ ፡ ይገዛል ፡፡

## ምዕራፍ ፲፪
## ጉባኤ

፩ ፤ ጥበብ ፡ ኢረከበት ፡ መካነ ፡ ኀበ ፡
ተኀድር ፤
ወልድ ፤ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፤
ሕግ ፡ ቦታ ፡ አላገኘችም ፤ ማግ
ኘትስ ፡ አግኝታ ፡ ነበር ፤ አዳምን ፡
በሕጉ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፡ ይሉት ፡
ነበር ፡ እንጂ ፡ ይበድላል ፡ ስላ
ላሉት ፤
ወሐለወ ፡ ማኀደራ ፡ ውስተ ፡ ሰማ
ያት ፤
ማደሪያዋ ፡ በመላእክት ፤ በእግዚ
አብሔር ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤
፪ ፤ ወጽአት ፡ ጥበብ ፡ ከመ ፡
ትኅድር ፡ ውስተ ፡ ውሉደ ፡ ሰብእ ፤
ሕግም ፡ በአዳም ፡ በልጆቹ ፡
ትኖር ፡ ዘንድ ፡ ተሰጠች ፤
ወኢረከበት ፡ ማኀደረ ፡ ጥበብ ፡
ውስተ ፡ መካና ፡ ገብአት ፤

ጥበብ ፡ ማደሪያዋን ፡ አላገኘችም፤ ወደ ፡ ማደሪያዋ ፡ ወደ ፡ መላእክት፡ ልቡና ፡ ተመለሰች ፤ ተነሥታ ቸው ፡ ኑሯ ፡ ማለት ፡ አይደ ለም ፤ እንደያዟት ፡ ቀሩ ፡ ሲል፡ ነው ፤

ወተጽዕነት ፡ ማዕከለ ፡ መላእክት ፤
በመላእክት፡ መካከል ፡ አደረች፤

፫ ፤ ወዓመፃ ፡ ወጽአት ፡ እመዛግ ብቲሃ፤

ክህደት፣ ኃጢአት ፣ ከዲያብሎስ ከአጋንንት ፡ ተገኘች ፤

ዘኢፈቀደት ፡ ረከበት ፤
ያልወደደችውን ፡ አገኘች ፣ መው ደድስ ፡ ወዳዋለች ፤ ሌሎች ፡ ሰዎች ፡ በሕጉ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖ ራል ፡ እንጂ ፡ ይበድላል ፡ ስላ ላሉት ፤ አንድም ፡ ዘፈቀደት ፡ ቢል ፡ የወደደችው ፡ ሕሊና ፡ አዳምን ፡ አገኘች ፤ አንድም ፡ ዘኢፈቀዳ ፡ ቢል ፡ ሕሊና ፡ ፈጣሪ ፡ ያልወደዳት ፡ ኃጢአት አዳምንና ፡ ሔዋንን ፡ አገኘች ፤

ውኀደረት ፡ ውስቴቶሙ ፡ ከመ ፡ ዝናም ፡ በበድው ፤ ወከመ ፡ ጠል ፡ በምድር ፡ ጽምዕት ፣
ዝናም ፡ በምድረ ፡ በዳ ፣ ጠል ፡ በተጠማች ፡ ምድር ፡ እንዲወ ደድ ፡ በእነርሱ ፡ ተስማማች ፤

፬ ፤ ወርኢኩ ፡ ካልዓነ ፡ መባርቅተ ፡ ወከዋክብተ ፡ ሰማይ ፤
ሌሎች ፡ መባርቅትን፣ የሰማይ ፡ ከዋክብትን፡ አየሁ ፡ አለ ፤ የመ ምህራን፡ ምሳሌ ፡ መባርቅትን ፤ የአርድዕትን ፡ ምሳሌ ፡ ከዋክብ ትን ፡ አየሁ ፤

፭ ፤ ወርኢኩ ፡ ከመ ፡ ይጼውዖሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ በበአስማቲሆሙ ፡ ወይሰም ዕዎ ፤
ሁሉንም ፡ በየስማቸው ፡ ሲጠራ ቸው ፣ እነሱም ፡ ሲሰሙት ፡ አየሁ ፡ አለ ፣ መምህራንን ፡ አርድዕት ፡ (ደቀ መዛሙርት)፡ ሲላቸው ፡ ሰማሁ ፤

፮ ፤ ወርኢክዎ ፡ ለመዳልወ ፡ ጽድቅ ፡ ከመ ፡ ይዴለዉ ፡ በብርሃናቲሆሙ ፡ በራሕበ ፡ መካናቲሆሙ ፤
ልቡናቸውን ፡ በአዕምሮ ፡ አስፍ ተው ፡ የሠሩት ፡ ሥራ ፡ በፍ ትሐ፡እግዚአብሔር ፡ ሲመጠን፣ ዋጋቸውን ፡ሲሰጣቸው ፡ አየሁ ፤

፯ ፤ ወዕለተ ፡ ኩነቶሙ ፤
በማኅፀን ፡ ከጨዋነት ፡ ወደ ፡ መምህርነት ፡ ወደ፡ ነቢይነት ፡ የተ መለሱበትን ፡ ቀን ፡ አየሁ ፤ እንደ ፡ ኤርምያስ ፣ እንደ ፡ ዮሐንስ ፡ ቀደስኩከ ፡ እምከርሠ፡ እምከ ፡ እንዳላቸው ፤

ወሚጠቶሙ ፤
ከጨዋነት ፡ ወደመምህርነት ፡ ወደነቢይነት ፡ የተመለሱበትን አየሁ ፤ እንደ ፡ ዮናስ ፡ እንደ አብድዩ ፤

መብረቅ ፡ መብረቀ ፡ ይወልድ ፤
መብረቅ ፡ መብረቅን ፡ ይወልዳል ፡ አለ ፣ መምህር ፡ መምህርን ፡ ያስገኛል፤

ወሚጠቶሙ ፡ በኍልቈ ፡ መላእክቲሆሙ ፤
ከጨዋነት ፡ ወደመምህርነት ፡ መመለሳቸው ፣ በመላእክተ ፡ ዑቃቤዎቻቸው ፡ ቊጥር ፡ነው፤ መልአከ ፡ ዑቃቢ ፡ እየራሱ ፡ የሌለው ፡ የለምና ፤ አንድም ፡ በዓቅመ ፡ መላእክት ፡ ቢል ፤ ከጨዋነት ፡ ወደ ፡ ነቢይነት ፡ መመለሳቸው ፡ በመምህሮቻቸው መጠን ፡ ነው ፤ አንድም ፡ በዓቅመ ፡ መላእክት ፡ ቢል ፡ ለእግዚአብሔር፡ ለመምህሮቻቸው ፡ እንደማገልገላ ቸው ፡ መጠን ፡ ነው ፤
ወሃይማኖቶሙ ፡ የዐቅቡ ፡ በበይና ቲሆሙ ፣
እርስ ፡ በርሳቸው ፡ መምህሮቹም ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ሃይማኖታ ቸውን ፡ ይጠብቃሉ ፤
፰ ፤ ወተስእልክዎ ፡ ለመልአክ ፡ ዘየሐውር ፡ ምስሌየ ፡ ወዘአርአየኒ ፡ ዘኅቡዕ ፡ ወእቤሎ ፡ ምንት ፡ እሙንቱ እሉ ፣
ከኔ ፡ ጋራ ፡ የሚኖረውን ፡ የተሰወ ረውንም ፡ የገለጠልኝን ፡ መልአ ኩን ፡ እኒህ ፡ ምንድን ፡ናቸው? ብዬ ፡ ጠየቅሁት ፤
፱ ፤ ወይቤለኒ ፡ ምስለ ፡ ዘዚአሆሙ ፡ አርአየከ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤
የመላእክት ፡ ጌታ ፡ የመምህራ ኑን ፡ ምሳሌ ፡ መባርቅትን ፣ የአ ርድዕትን ፡ ምሳሌ ፡ ከዋክብትን ፣ አሳየህ፤ አንድም ፡ የመምህራኑ ፡ ምሳሌ የሚሆኑ ፡ አርድዕትን ፣ የአርድዕት ፡ አብነት ፡ የሚሆኑ፡ መምህራኑን ፡ አሳየህ ፤አንድም፡ ምስለ ፡ ዘዚአሆሙ ፡ ቢል ፡ ከመምህራኑ ፡ ጋራ ፡ የሚኖሩ፡ አርድዕትን ፣ ከአርድዕት ፡ ጋራ ፡ የሚኖሩ ፡ መምህራኑን ፡ አሳየህ ፡ አለኝ፤
እሉ ፡ እሙንቱ ፡ አስማቲሆሙ ለጻድቃን ፤
የመምህራኑ ፣ የአርድዕቱ ፡ ስማ ቸው ፡ ይኸ ፡ ነው ፤
እለ ፡ የኃድሩ ፡ ዲበ ፡ የብስ ፣
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያሉ ፤
ወየአምኑ ፡ በስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መና ፍስት ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፣
በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስም ፡ ለዘ ለዓለሙ ፡ የሚያምኑ ፣ ያመኑ ፡ የጻድቃን ፡ ስማቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፤
፲ ፤ ወካልዕተ ፡ ርኢኩ ፡ በእንተ፡ መብ ረቅ ፤
ስለ ፡ መብረቅ ፡ ሌሎች ፡ ራእ ዮችን ፡ አየሁ ፡ አለ ፤ የመምህ ራኑን፡ ነገር ፡ አየሁ ፤
እፎ ፡ ይቀውሙ ፡ እምከዋክብት ፣
ከደቀ ፡ መዛሙርቱ ፡ መምህራን እየሆኑ ፡ ሲነሡ ፡ አየሁ ፤
ወይከውኑ ፡ መብረቀ ፤
መምህራን ፡ ሲሆኑ ፡ አየሁ ፤
ወኢይክሉ ፡ ኀዲገ ፡ ምስሌሆሙ ፤
መባርቅት፡ የመምህራኑ ፡ ምሳሌ፤ ከዋክብት፡ የአርድዕት ፡ ምሳሌ ፣

መሆንን፡ መተው ፡ አይችሉም፤
አንድም፡ መምህራኑ፡ ለአርድዕት
አብነት ፡ መሆንን ፣ አርድዕት ፡
ለመምህራን ፡ ምሳሌ ፡ መሆንን ፡
መተው ፡ አይችሉም ፤ አንድም
ምስሌሆሙ ፡ ቢል ፡ መምህራን
ከአርድዕት ፡ ጋራ ፣ አርድዕት ፡
ከመምህራን ፡ ጋራ ፡ መኖር ፡
መተውን ፡ አይችሉም ፤
፲፩ ፤ ወዝ ፡ ካልዕ ፡ ምሳሌ ፡ ዲበ ፡
እለ ፡ ይክህዱ ፡ ስሞ ፡ ለማኅደረ ፡
ቅዱሳን፤
የቅዱሳን ፡ ማደሪያ ፡ የሚሆን ፡
የክርስቶስን ፡ ስም ፡ በሚክዱ ፣
ወለእግዚአ ፡ መናፍስት ፤
የአብን፡ ስም ፡ በሚክዱ ፡ ሰዎች
የተነገረው ፡ ሁለተኛ ፡ ነገር ፡
ይህ ፡ ነው ፤
፲፪ ፤ ኢሰማየ ፡ የዐርጉ ፣
ወደ ፡ ሰማይ ፡ አይወጡም ፤
ወኢምድረ ፡ ይበጽሑ ፤
ወደ ፡ ምድርም፡ አይደርሱም ፤
ኑሯቸው ፡ በጎዋው ፡ ነው ፤ ላገ
ኛቸው ፡ መከራ ፡ ፍጻሜ ፡ እን
ደሌለው ፡ ለማጠየቅ ፡ ነው፤
ከመዝ ፡ ይከውን ፡ ክፍለ ፡ ኃጥአን ፡
እለ ፡ ይክህዱ ፡ ስሞ ፡ ለእግዚአ ፡
መናፍስት ፤
የመላእክትን ፡ ጌታ ፡ ስም ፡
የሚክዱ ፡ የኃጢአተኞች ፡ ዕድል ፡
እንዲህ ይሆናል ፤
እለ ፡ ከመዝ ፡ ይትዐቀቡ ፡ ለዕለተ
ሥራሕ ፡ ወምንዳቤ ፣
ፍጹም ፡ መከራ ፡ በሚደረግበት ፡
ቀን ፡ እንዲህ ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡
ከብዙ ጣር ፡ ጋር ፡ ለመከራ ፡
ቀን ፡ ይጠበቃሉ ፤
ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ ይነብር ፡
በመንበረ ፡ ስብሐት ፡ ኅሩይ ፣
በዚህች ፡ ቀን ፡ ኅሩይ ፡ ክርስቶስ
በጌትነቱ፡ ዙፋን ፡ ይቀመጣል ፤
፲፫ ፤ ወየኀሪ ፡ ምግባሪሆሙ ፡ ወም
ዕራፎሙ ፡ወኍልቆ ፡አልቦሙ ፣
ሥራቸውንም ፡ ቦታቸውንም ፡
ይመረምራል ፤ ቍጥር ፡ የላቸ
ውም ፣ በመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡
ለሚኖሩት ፡ አነዋወር ፡ ፍጻሜ
የለውም ፡
፲፬ ፤ ወመንፈሶሙ ፡ በማዕከሎሙ ፡
ትጸንዕ ፡ ሶበ ፡ ርእይዎ ፡ ለኅሩየ ፡
ዚአየ ፤
በመካከላቸው ፡ ያለች ፡ ልቡናቸው፡
የመረጥሁት ፡ ክርስቶስን ፡ ባዩት ፡
ጊዜ ፡ ትጸናለች ፤
፲፭ለእለ ፡ ይሰክዩ ፡ ስምየ ፡ ቅዱሰ ፡
ወስቡሐ ፤
ስሜን ፡ የሚማፀኑ ፣ ስሜን ፡
ያመኑ ፡ ባዩት ፡ ጊዜ ፤
፲፮ ፤ ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ አነብሮ ፡
ለኅሩየ ፡ ዚአየ ፡ በማዕከሎሙ ፤
በዚያችም ፡ ቀን ፡ የመረጥሁት
ክርስቶስን ፡ በመካከላቸው ፡ አኖረ
ዋለሁ ፡ አለ ፤
፲፯ ፤ ወእዌልጣ ፡ ለሰማይ ፣
ሰማይን ፡ አሳልፋታለሁ ፤
ወእገብራ ፡ ለበረከት ፣

መንግሥተ ፡ ሰማይን ፡ ለበረከተ፡ ነፍስ ፡ አደርጋታለሁ ፤

ወብርሃን ፡ ዘለዓለም ፤

ለዘለዓለም ፡ የሚኖር ፡ የመንግ ሥተ ፡ ሰማይ ፡ ብርሃን ፡ ጸንቶ ይኖራል ፤

ወእዌልጣ ፡ ለየብስ ፡ ወእገብራ ፡ ለበረከት ፤

ምድርን ፡ አሳልፋታለሁ ፤ የም ትመጣ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይን ቁም ፡ ነገር ፡ አደርጋታለሁ ፤

፲፯ ፤ ወለኅሩያን ፡ ዚአየ ፡ እነብ ሮሙ ፡ ውስቴታ ፤

ወዳጆቼን ፡ በውስጧ ፡ አኖራቸ ዋለሁ ፤

ወእለሰ ፡ ይገብሩ ፡ ኀጢአተ፤ ወጌጋየ፤ ሁለቱ፡ አርእስት ፡ ነው ፤ ለሁለ ቱም ፡ ያመጣል ፡

ኢይከይዱ ፡ ውስቴታ ፤

ኪያሃ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ ኀጢአት የሚሠሩ ፡ ሰዎች ፡ እርሷን ፡ አይረግጡም ፤ ወደ ፡ እርሷ ፡ አይገቡም ፤

እስመ ፡ አነ ፡ ርኢክዎሙ ፤

በዓይነ ፡ ምሕረት ፡ አይቻቸዋ ለሁና ፤

ወአጽገብክዎሙ ፡ በሰላም ፡ ለጻድ ቃንየ ፤

ለወዳጆቼ ፡ ጸጋውን ፡ ክብሩን አጥግቤያቸዋለሁና ፡ አነብሮሙ ላለው ፤

ወአንበርክዎሙ ፡ ቅድሜየ ፤

በፊቴም ፡ በባለሟልነት ፡ አኖር ኋቸው ፡

፲፰ ፤ ወቀርበት ፡ ኅቤየ ፡ ኰነኔ ፡ ለኃጥአን ፡ ከመ ፡ አኅጕሎሙ ፡ እምገጸ ፡ ምድር ፤

ከመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ አጠፋቸው ፡ ዘንድ ፡ ፍርዴ ፡ ወደእኔ ፡ ቀርባለችና ፡ ኢይከይዱ ፡ ላለው ፤

፲፱ ፤ ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ ዘሎቱ ፡ ርእሰ ፡ መዋዕል ፤

ብሉየ ፡ መዋዕልነት ፡ ገንዘቡ ፡ የሚሆን ፤ አንድም ፡ ከስድስቱ ፡ ዕለታት ፡ የሚቀድም ፡ ዕለተ ፡ እሑድ ፡ ገንዘቡ ፡ የሚሆን ፡ አብን ፡ አየሁ ፡ ሲል ፡ ነው ፤

ወርእሱ ፡ ከመ ፡ ፀምር ፡ ፀዓዳ ፤

ራሱ ፡ ቅሉ ፡ እንደ ፡ ብዝት ፡ ነጭ ፡ ነው ፤ ንጹሐ፡ ባሕርይ ፡ ነኝ ፡ ሲል ፤

፳ ፤ ወምስሌሁ ፡ ካልዕ ፡ ዘገጹ ፡ ከመ ፡ ርእየተ ፡ ሰብእ ፤

መልኩ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ፊት ፡ ያለ ፡ ሌላ፡ ከእርሱ ፡ አየሁ ፡ ለለ፡ ወልድ፡ ነው ፤

ወምሉዕ ፡ ጸጋ ፤

የባሕርይ ፡ ክብሩን ፡ ለሰው ፡ የሚ ሰጠው ፡ ስለሆነ ፡ ጸጋ ፡ ብሎታል ፡ ወዘመለኮቱ ፡ ጸጋ ፡ ምሉዕ ፡ ወኢን ሥአ ፡ ጸጋ ፡ እምካልአዕ ፡ አምላክ* ፡ እንዲል ፤

ወገጹ ፡ ከመ ፡ ፩ እመላእክት ፡ ቅዱ ሳን ፤

ፊቱ ፡ ከቅዱሳን ፡ መላእክት ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ ነው ፤ የመላእክትና ፡

---

፩ ፤ ሃይማኖተ ፡ አበው ፤

የሰው ፡ ተሥዕሎተ ፡ መልክዐ ፡ አንድ ፡ ነውና ፤ አንድም ፡ ከኪሩቤል እንደ ፡ አንዱ ፡ ነው ፡ አለ ፤ እንደ ፡ ገጸ ፡ ሰብእ ፡ ነው ፤ አንድም ፡ እንደ ፡ ቅዱስ ፡ ገብርኤል ፡ ነው ፡ አለ ፤ ገብርኤል ፡ ማለት ፡ አምላክ ፡ ወሰብእ ፡ ማለት ፡ ነውና ፤

፻፩ ፤ ወተስእልክዎ ፡ ለአሐዱ ፡ እመላእክት ፡ ቅዱሳን ፡ ዘየሐውር ፡ ምስሌየ ፡ ወኵሎ ፡ ኅቡአተ ፡ ዘአርአየኒ ፡ በእንተ ፡ ዝኩ ፡ ወልደ ፡ ሰብእ ፤

ከእኔ ፡ ጋራ ፡ የሚኖር ፡ የተሰወረውንም ፡ ሁሉ ፡ የገለጠልኝ ፡ ከከበሩ ፡ መላእክት ፡ አንዱን ፡ ከሰው ፡ የተወለደ ፡ የዚህን ፡ የክርስቶስን ፡ ነገር ፡ ጠየቅሁት ፤

፻፪ ፤ ወእቤሎ ፡ መኑ ፡ ውእቱ ወእምአይቴ ፡ ይከውን ፡ ውእቱ ፡ ወበእንተ ፡ ምንት ፡ ምስለ ፡ ርእሰ ፡ መዋዕል ፡ የሐውር ፤

ይህ ፡ ማነው ? ከወዴትስ ፡ ተገኘ ? ከብሉየ ፡ መዋዕል ፡ ከአብ ፡ ጋራ ፡ ስለምን ፡ ተቀመጠ ፡ ብዬ ፡ ጠየቅሁት ፡

፻፫ ፤ ወአውሥአኒ ፡ ወይቤለኒ ፡ ዝንቱ ፡ ውእቱ ፡ ወልደ ፡ ሰብእ ፡ ዘሎቱ ፡ ኮነ ፡ ጽድቅ ፤

ትንቢት ፡ የተነገረለት ፡ ከሰው ፡ የተወለደው ፡ ክርስቶስ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ መለሰልኝ ።

ወጽድቅ ፡ ምስሌሁ ፡ ኃደረ ፤

ትንቢት ፡ የተፈጸመለት ፤ አንድም ፡ ትንቢት ፡ የተነገረለት ፡ የተፈጸመለት ፡ ይህ ፡ ነው ፡ አለኝ ።

አንድም ፡ ወጽድቅ ፡ ምስሌሁ ፤ የባሕርይ ፡ ክብሩ ፡ ገንዘቡ ፡ የሚሆን ፤

ወኵሎ ፡ መዛግብተ ፡ ዘኅቡዕ ፡ ውእቱ ፡ ይከሥት ፡ እስመ ፡ እግዚአ መናፍስት ፡ ኪያሁ ፡ ኀረየ ፤

አብ ፡ ክርስቶስን ፡ መርጧልና ፤ ክርስቶስ ፡ የተወሐደው ፡ ሥጋን መርጧልና ፤ እርሱ ፡ የተሠወረውን ፡ ምሥጢር ፡ ይገልጣል ፤

፻፬ ፤ ወዘክፍሉ ፡ ኮሎ ፡ ሞአ ፤

ዕድሉ ፡ ሥጋ ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፈቃድ ፡ ሁሉን ፡ ድል ፡ ያደረገ ፤

በርትዕ ፡ ለዓለም ፤

ለዘለዓለም ፡ በሚገባ ፡ ነው ፤ ተዋሕዶ ፡ በሠራው ፡ ሥራ ፡ ነው ፤ አንድም ፡ ወዘኮሎ ፡ ሞዐ ፡ ይላል ፤ ኃጣውእን ፡ አጋንትን ፡ ድል ፡ ያደረገ ፡ በለበሰው ፡ ሥጋ ፡ ነው ፤

፻፭ ፤ ወዝንቱ ፡ ወልደ ፡ ሰብእ ዘርኢከ ፡ ያነሥኦሙ ፡ ለነገሥት ወለኃያላን ፡ እምስካባቲሆሙ ፡ ወለጽኑዓን ፡ እመናብርቲሆሙ ፤

ይህ ፡ ያየኸው ፡ ወልደ ፡ አዳም ኃያላኑን ፡ ከሹመታቸው ፡ ይሽራቸዋል ፤ ጽኑዓኑንም ፡ ከዙፋናቸው ፡ ያወርዳቸዋል ፤

፳፮ ፡ ወይፈትሕ ፡ ልጓማተ ፡ ጽኑዓን ፡

የኃያላኑን ፡ ሥልጣን ፡ ሲያሳል ፈው ፡ አየሁ ፡ ሲል ፡ ነው ፡ ልጓማት ፡ ጽኑዓን ፡ ቢል ፡ ጽኑ ጽኑውን ፡ ሥልጣን ፡ ያሳልፋል ፡

ወያደቅቅ፡ አስናነ ፡ ኃጥአን ፡

የኃጥአንንም ፡ ጥርሶች ፡ ይሰብ ራል ፡ ማለት ፡ ሥልጣናቸውን ፡ ያጠፋል ፡

ወይገፈትዖሙ ፡ ለነገሥት ፡ እመና ብርቲሆሙ ፡ ወእመንግሥቶሙ ፡

ነገሥታቱንም ፡ ከዙፋናቸው ፡ እየገለበጠ ፡ ይጥላቸዋል ፡ ከመ ንግሥታቸውም ፡ ይለያቸዋል ፡

እስመ፡ ኢያሌዕልዎ፡ ወኢይሴብሕዎ ፡ ወኢይገንዩ ፡

አክብረው ፡ አላመሰገኑትምና ፡ ለእርሱም ፡ አይገዙለትም ፡

ወእምአይቴ ፡ ተውህበት ፡ ሎሙ ፡ መንግሥት ፡

መንግሥት ፡ ከወዴትም ፡ እንደ ተገኘች ፡ አውቀው ፡ ከእርሱም ፡ እንደተገኘች ፡ አውቀው ፡ አይገዙ ለትም ፡ መንግሥት ፡ ከወዴት ፡ አገኘን ፡ ይመስላቸዋል?

፳፯ ፡ ወገጸ ፡ ጽኑዓን ፡ ይገፈትዕ ፡ ወይመልዖሙ ፡ ኃፍረተ ፡ ወጽልመተ ፡ ይከውኖሙ ፡ ማኅደሪሆሙ ፡

የጽኑ ፡ ሰዎች ፡ ሰውነትን ፡ ያጠፋል ፡ ኃፍረትንም ፡ ይመላቸ ዋል ፡ ማደሪያቸው ፡ ጨለማ ፡ ይሆንባቸዋል ፡

፳፰ ፡ ወዕፄያት ፡ ይከውንዎሙ ፡ ምስካቢሆሙ ፡

መኝታቸው፡ ትሎች ፡ ይሆናሉ፡ አለ ፡ ዕፄሁ ፡ ዘኢይነውም ፡ ወእሳቱ ፡ ዘኢይጠፍዕ ፡ ያለው ፡ ነው ፡

ወኢይሴፈዉ ፡ ከመ ፡ ይትነሥኡ ፡ እምስካባቲሆሙ ፡

ከመቃብርም ፡ ይነሡ ፡ ዘንድ ፡ ተስፋ ፡ አላደረጉም ፡ ትንሣኤያ ቸው ፡ ዘለኃሣር ፡ ስለሆነ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ መነሣትስ ፡ ይነሣሉ ፡ አንድም ፡ ከገሃነም ፡ እንወጣለን ፡ ብለው ፡ ተስፋ ፡ አያደርጉም ፡

እስመ ፡ ኢያሌዕሉ ፡ ስሞ ፡ ለእግዚአ መናፍስት ፡

የመላእክትን ፡ ጌታ ፡ ስም ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አላደረጉምና ፡

፳፱ ፡ ወእሙንቱ ፡ ኮኑ ፡ እለ ፡ ይኴንኑ ፡ ከዋክብተ ፡ ሰማይ ፡

እነሱም ፡ ጻድቃንን ፡ የሚበድሉ ሁነዋልና ፡

ወያሌዕሉ ፡ እደዊሆሙ ፡ ውስተ ፡ ልዑል ፡

ቃላቸውንም ፡ ወደ ፡ እግዚ አብሔር፡ ያደርሳሉና ፡

ወይከይዱ ፡ ዲበ ፡ የብስ ፡

ይህችንም ፡ ዓለም ፡ ይገዛሉና ፡

ወየኀድሩ ፡ ውስቴታ ፡

በዚህችም ፡ ዓለም ፡ በተድላ ፡ በደስታ፡ ጸንተው ፡ ይኖራሉና፡

፴ ፡ ወኵሎ ፡ ተግባሮሙ ፡ ዓመፃ ፡ ያሬእዩ ፡

የዓመፅ ፡ ሥራቸውን ፡ የሚገልጹ ፡ ሁነዋል ።
ወኵሉ ፡ ተግባሮሙ ፡ ዓመፃ ።
ሥራቸውም ፡ ሁሉ ፡ በደል ፡ ነውና ።
ወኃይሎሙ ፡ ዲበ ፡ ብዕሎሙ ።
ኃይላቸው ፡ በባለጸግነታቸው ፡ ላይ ፡ ነው ። ብዕላችን ፡ ያልፋል ፡ አይሉምና ። ማደሪያቸው ፡ ጨለማ ፡ ይሆናል ።
፲፭ ። ወሃይማኖቶሙ ፡ ኮነ ፡ ለአማልክት ፡ እለ ፡ ገብሩ ፡ በእደዊሆሙ ።
ሃይማኖታቸው ፡ በእጃቸው ፡ ለሠሯቸው ፡ ለጣዖታቱ ፡ ሁኗልና ።
ወይክህዱ ፡ ስሞ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ።
የመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስሙንም ፡ ክደዋል ፡
፲፮ ። ወይሰደዱ ፡ እምአብያት ። ምስትጉቡአ ፡ ዚአሁ ።
አብያት ፡ ምስትጉቡእ ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ነው ። ከሚወርሳት ፡ ከመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ይሰደዳሉ ። እንድም ፡ በየራሱ ፡ ለማውጣት ፡ ማደሪያቸው ፡ ከሚሆኑ ፡ ጻድቃን ፡ ከሚወርሷት ፡ ከመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ይሰደዳሉ ።
ወለመሃይምናን ፡ እለ ፡ ስቁላን ፡ በስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፡
በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስም ፡ አምነው ፡ የሠሩት ፡ ሥራ ። እንድም ፡ በስሙ ፡ ቢያምኑ ፡ ያደረገላቸው ፡ ክብር ፡ ጸንቶላቸው ፡ የሚኖሩ ፡ ጻድቃን ፡ ከሚወርሷት ፡ ከመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ይሰደዳሉ ።

## ጉባኤ

፲፯ ። ወበውእቱ ፡ መዋዕል ፡ ዐርገት ፡ ጸሎተ ፡ ጻድቃን ።
ለጻድቃን ፡ ፈርዶ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያትን ፡ ባወረሰባት ። በኃጥአን ፡ ፈርዶ ፡ ገሃነመ ፡ እሳትን ፡ ባወረሰባት ፡ በዚያ ፡ ቀን ፡ የጻድቃን ፡ ጸሎት ፡ ወደ ፡ አብ ፡ ደረሰች ። አንድም ፡ ዋጋ ፡ አሰጠች ።
ወደመ ፡ ጻድቅ ፡ እምነ ፡ ምድር ፡ ቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ተፈቅደ ።
የጻድቁ ፡ ደም ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ ተወደደ ፡ አለ ። ዋጋ ፡ አሰጠ ። አንድም ፡ የጻድቀ ፡ ባሕርይ ፡ የክርስቶስ ፡ ደም ፡ ለምዕመናን ፡ የምግባር ፡ የሃይማኖታቸውን ፡ ዋጋ ፡ አሰጠ ።
፲፰ ። ወበእሉ ፡ መዋዕል ፡ የኀብሩ ፡ ቅዱሳን ፡ እለ ፡ ይነብሩ ፡ መልዕልተ ፡ ሰማያት ፡ በአሐዱ ፡ ቃል ።
በሰማይ ፡ ያሉ ፡ መላእክት ፡ በአንድ ፡ ቃል ። ከጻድቃን ፡ ጋራ ፡ ይተባበራሉ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ በማለት ፡ ነው ።
ያስተበቍዑ ፡ ወይጼልዩ ፡ ወይሴብሑ ።
ለሰው ፡ ፈጽመው ፡ ይለምናሉ ። ፈጣሪያቸውንም ፡ ያመሰግናሉ ።
፲፱ ። ወየአኵቱ ፡ ወይባርኩ ፡ በስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ በእንተ ፡ ደመ ፡ ጻድቃን ፡ ዘተክዕወ ።

በግፍ ፡ የፈሰሰ ፡ የጻድቃን ፡ ደም፡ዋጋ፡ ስለአሰጠ ፡ ፈጽመው ፡ ያመሰግናሉ ፤
፴፮ ፤ ወበጸሎቶሙ ፡ ለጻድቃን ፡ ከመ ፡ ኢትጸራዕ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤
በአብ፡ ፊት ፡ የቅዱሳን፡ ጸሎት፡ የቦዘነች ፡ ሁና ፡ በከንቱ ፡ እንዳ ትቀር ፣ ዋጋ ፡ ሳታሰጥ ፡ እንዳ ትቀር ፤
ከመ ፡ ይትገበር ፡ ሎሙ ፡ ኵነኔ ፤ ለጻድቃን፡ፍርድ ፡ይደረግባቸው፤ ዘንድ ፣ ኢይትገበር ፡ ቢል ፡ ፍርድ፡እንዳይደረግባቸው፤
ወትዕግሥት ፡ ኢይኩን ፡ ሎሙ ፡ ለዓለም ፤
ለዘለዓለሙ፡ ቸልታ ፡ እንዳይደረ ግባቸው ፣ ይኩን ፡ ቢል ፡ ታግሶ፡ ታግሶ ፡ ዋጋቸውን፡ ይሰጣቸው፡ ዘንድ ፤
፴፯ ፤ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ርኢ ክዎ ፡ ለርእሰ ፡ መዋዕል ፡ ሶበ ፡ ነበረ ፡ በመንበረ ፡ ስብሐቲሁ ፤
በነዚያም ፡ ወራቶች ፡ ብሉየ ፡ መዋዕልነት ፡ ገንዘቡ ፡ የሆነ ፡ ጌታን ፡ በጌትነቱ ፡ ዙፋን ፡ ተቀ ምጦ ፡ አየሁት ፤
ወመጻሕፍተ ፡ ሕያዋን ፡ ተከሥቱ ፡ በቅድሜሁ ፣
በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሕያዋን ፡ የሚሆኑ ፡ ነቢያት ፣ ሐዋርያት፣ የጻፏቸው ፤ ብሉያት ፣ ሐዲሳት ፣ ይነበባሉ ፤ ይተረጐማሉ ፤ እየተ ተረጐሙ ፡ በዚያ ፡ የተጻፈውን፡ ምግባር ፡ ሃይማኖት ፡ የሠራ ፡ በዚያ ፡ የተጻፈውን ፡ ዋጋ ፤ በዚያ ፡ የተጻፈውን ፡ ኃጢአት ፡ የሠራ ፤ በዚያ ፡ የተጻፈውን ፡ ፍዳ ፡ ይቀበላልና ፣ በዚያስ ፡ ጊዜ ፡ መነበብ ፡ መተርጐም ፡ የለም ፡ ብሉ ፡ ዛሬ ፡ የሚነ በበው ፣ የሚተረጐመው ፡ ኋላ ፡ የሚፈጸም ፡ ስለሆነ ፡ ነው ፤
አንድም ፡ ምግባረ ፡ ጻድቃን ፡ ምግባረ፡ኃጥአን ፡ ይመረመራል፤
፴፰ ፤ ወኵሉ ፡ ኃይሉ ፡ ዘመል ዕልተ ፡ ሰማያት ፡ ዓውደ ፡ ዚአሁ ፡ ይቀውሙ ፡ ቅድሜሁ፤
በሰማይ ፡ በዙሪያው ፡ ያሉ ፡ መላእክት ፡ በፊቱ ፡ ይቆማሉ ፤ በዘፈቀደ ፡ ይታያልና ፡ ዓውደ ፡ ዚአሁ ፣ ለእግዚአብሔር ፡ ሁሉ ፡ ቅድሙ፡ነውና፡ቅድሜሁ፡አለ፤
፴፱ ፤ ወልበሙ ፡ ለቅዱሳን ፡ ትመ ልዕ ፡ ፍሥሓ ፡ እስመ ፡ በጽሐ ፡ ጐልቁ ፡ ለጽድቅ ፤
የቅዱሳን ፡ ልባቸው ፡ ደስታን ፡ ትመላለች ፣ የጽድቅ ፡ ምግባርዋ፡ ደርስዋልና ፣
ወጸሎቶሙ ፡ ለጻድቃን ፡ ተሰምዐ ፤
የጻድቃንም ፡ ልመናቸው ፡ ተሰ ምቷልና ፡ ልቡናቸው ፡ ተድላ ፡ ደስታን ፡ ትመላለች ፤ ጐልቊ ፡ ለጽድቅ፡ሲል፡ሃይማኖት ፣ምግ ባር ፡ ዋጋ ፡ የምታሠጥበት ፡ ጊዜ፡ደርሷልና፤የኢታምልክም ፡ ቍጥሯ ፡ ደርሷልና ፤
፵ ፤ ወደሙ ፡ ለጻድቅ ፡ በቅድመ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ተፈቅደ ፣ የጻድቅ ፡ ደም ፡ በአብ ፡ ፊት ፡ ተወደደ ፡ አለ ፤ ዋጋ ፡ አሰጥ ቷል ፤ አንድም ፡ የወልድ ፡ ደሙ ፡ በአብ ፡ ፊት ፡ ለምዕመ ናን ፡ ዋጋ ፡ አሰጥቷልና ፡፡

## ምዕራፍ ፲፫

፩ ፤ ወበውእቱ ፡ መካን ፡ ርኢኩ ፡ ነቅዓ ፡ ጽድቅ ፡ ዘኢይትኌለቍ ፤
ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የሌለው ፡ የጽድቅ ፡ ምንጭን ፡ አየሁ፤ እንድም ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የሌለው ፡ የምሥጢር ፡ መገኛ ፡ ኦሪትን ፡ አየሁ ፤ እንድም ፡ ወንጌልን ፡ አየሁ፤

፪ ፤ ወበዐውዱ ፡ የአውድዎ ፡ ብዙኃን ፡ አንቅዕተ ፡ ጥበብ ፤
ጥበብን ፡ የሚገልጹ ፡ አንቅዕት (ምንጮች)፡ ዙሪያውን ፡ ይከቡታል ፤ እንድም ፡ ኦሪትን ፡ መጻሕፍተ ፡ ነቢያት ፤ ወንጌልን ፡ መጻሕፍተ ፡ ሐዲሳት ፡ ይከቡታል ፤
ወኵሎሙ ፡ ጽሙኣን ፡ ሰትዩ ፡ እምኔሁ፤
ከትምህርት ፡ ከዕውቀት ፡ የተጠሙ ፡ ሰዎች ፡ ከእርሱ ፡ ይጠጣሉ ፤
ወይትመልኡ ፡ ጥበበ ፤
ጥበቡንም ፡ ይማሩታል ፤

፫ ፤ ወማኅደሪሆሙ ፡ ምስለ ፡ ጻድቃን ፡ ወቅዱሳን ወኅሩያን ፤
ብሉያትን፡ ሐዲሳትን ፡ ተምረው ከግብር ፡ ገብተው ፡ ሥራ ፡ የሠሩ ፡ ሰዎች ፡ መኖሪያቸው ፡ ከመላእክት ፡ ጋራ ፡ ነው ፤

፬ ፤ ወበይእቲ ፡ ሰዓት ፡ ተጸውዐ ፡ ዝኩ ፡ ወልደ ፡ ሰብእ ፡ በኀበ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤
በዚያችም ፡ ሰዓት ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ዘንድ ፡ ከሰው ፡ የተወለደ ፡ ወልደ ፡ ሰብእ ፡ ክርስቶስ ተጠራ ፤

፭ ፤ ወስሙ ፡ መቅድመ ፡ ርእሰ ፡ መዋዕል ፤
መቅድም ፡ ርእስ ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ነው ፤ ብሉየ ፡ መዋዕል ፡ ተባለ ፤ እንድም ፡ ከስድስቱ ፡ ዕለታት ፡ ከምትቀድም ፡ ከዕለተ እሑድ ፡ አስቀድሞ ፡ የነበረ ፡ ተባለ ፤

፮ ፤ ወዘእንበለ ፡ ይትፌጠር ፡ ፀሐይ ፡ ወተአምር ፤
ከፀሐይ ፡ ከጨረቃ ፡ አስቀድሞ፡ የነበረ ፡ ተባለ ፤ ወትእምርት ፡ ለብሔር[፩] ፡ እንዲል ፤
ወዘእንበለ ፡ ይትገበሩ ፡ ከዋክብተ ፡ ሰማይ ፡ ተጸውአ ፡ ስሙ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤
ፀሐይ ፡ ሳይፈጠር ፡ ጨረቃም ፡ ሳይፈጠር ፡ በሰማይ ፡ ያሉ ፡ መላእክትም ፡ ሳይፈጠሩ ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ ስሙ ፡ ብሉየ ፡ መዋዕል ፡ ተባለ ፤

---

፩፤ ሲራ ፡ ፵ ፡ ፮

፯ ፤ ወውእቱ ፡ ይከውን ፡ በትረ ፡ ለጻድቃን ፡ ወለቅዱሳን ፤
ለደናግል ፡ ለሕጋውያን ፡ ኃይል ጽንዕ ፡ ይሆናል ፤
ከመ ፡ በቱ ፡ ይትመረጐዙ ፡ ወከመ ኢይደቁ ፤
በኃጢአት ፡ በክህደት ፡ እንዳይ ሰነካከሉ ፡ በእርሱ ፡ ጸንተው ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ ፤
ወውእቱ ፡ ብርሃነ ፡ አሕዛብ ፡ ወው እቱ ፡ ይከውን ፡ ተስፋ ፡ ለእለ ፡ የሐምሙ ፡ በልቦሙ ፤
የአሕዛብ ፡ ብርሃን ፡ ጸጋቸው ፤ አንድም ፡ መምህራቸው ፡ እሱ ፡ ነው ፤ ኃጢአት፡ሠርተው ፡ በል ባቸው ፤ ለሚያዝኑም ፡ ሰዎች፡ አለኝታ ፡ ይሆናቸዋል ፤
፰ ፤ ወይወድቁ ፡ ወይሰግዱ ፡ ቅድ ሜሁ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ የኀድሩ ፡ ውስተ ፡ የብስ ፤
በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ ወድቀው ፡ ይሰ ግዱሉ ፤
ወይባርክዎ ፡ ወይሴብሕዎ ፡ ወይዜ ምሩ ፡ ሎቱ ፡ ለስመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤
ፈጽመውም ፡ ያመሰግኑታል ፤ ለመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስምም ፡ ምስጋናን ፡ ያቀርቡለታል ፤
፱ ፤ ወበእንተዝ ፡ ኮነ ፡ ኅሩየ ፡ ወኅቡዐ ፡ በቅድሜሁ ፡ እምቅድመ ፡ ይትፈጠር ፡ ዓለም ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም፤
ኮነነ ፡ ሲል ፡ ነው ፡ ስለዚህም ፡ ነገር ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ፡እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ድረስ ፡ አስታራቂ ፡ሆነን ፤ የተ ሠወረም ፡ ሆነ ፤ አንድም ፡ ወኀ ቡዐ ፡ በቅድሜሁ ፤ በአብ ፡ ፊት ፡ የተሠወረ ፡ ሆኗልና ፡ እለ ፡ ክርስቶስን ፡ ነው ፤
፲ ፤ ወከሠቶ ፡ ለቅዱሳን ፡ ወለጻድ ቃን፡ ጥበቡ ፡ ለእግዚአ ፡መናፍስት ፤
የእግዚአብሔር ፡ የባሕርይ ፡ ጥበቡ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በዘ መነ ፡ ሥጋዌ ፡ ወልድን ፡ ለሐ ዋርያት፡ ለምዕመናን ፡ ገለጸው፤
እስመ ፡ ዐቀበ ፡ ክፍሎሙ ፡ ለጻ ድቃን ፤
የሐዋርያትን ፡ የምዕመናንን ፡ ዕድል ፡ ፈንታ ፡ ክብር ፤ ልጅ ነትን ፡ ጠብቋልና ፤ አንድም ፡ ወከሠቶ ፤ ለደናግል ፡ ለሕጋ ውያን ፡ በምጽአት ፡ ክርስቶስን ገለጸው ፤ እስመ ፡ ዓቀበ ፤ ዕድ ላቸው ፡መንግሥተ ፡ ሰማይን ፡ ጠብቆላቸዋልና ፤
፲፩ ፤ እስመ ፡ ጸልዕዎ ፡ ወመ ነንዎ ለዝ ፡ ዓለም ፡ ዘዓመፃ ፤
ይህን ፡ የበደል ፡ ዓለም ፡ ፈጽ መው ፡ ስለ ፡ ጠሉት ፤
ወኵሎ ፡ ምግባሮ ፡ ወፍናዊሁ ፡ ጸልዑ ፡ በስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፤
ግፍ ፡ የሚሠራበት ፡ ይህን ፡ ዓለም ፡ ንቀው ፡ ጠልተውታ ልና ፤ ሹመቱን ፡ ሽልማቱን ፡

ሁሉ ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስም ፡ አምነው ፡ ሥራውን ፡ ሁሉ ፡ ጠልተውታልና ፤

፯ ፤ እስመ ፡ በስመ ፡ ዚአሁ ፡ ይድኅኑ ፡ ወፈቃዴ ፡ ኮነ ፡ ለሕይወቶሙ ፤

በስሙ ፡ አምነው ፡ ይድናሉ ፡ ድኅነታውን ፡ የሚወድ ፡ሁኗልና ፤

፰ ፤ ወበውእቱ ፡ መዋዕል ፡ ኮኑ ፡ ትሑታነ ፡ ገጽ ፡ ነገሥተ ፡ ምድር ፡ ወጽኑዓን ፤

ለጻድቃን ፡ ፈርዶ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይን ፡ በሚያወርስበት ፤ በኃጥአን ፡ ፈርዶ ፡ ገሃነመ ፡ እሳት ፡ በሚያወርድበት ፡ ጊዜ ፡ ነገሥታት ፡ ያዘኑ ፡ ሆኑ ፤

እለ ፡ ይእኅዝዋ ፡ ለየብስ ፤

ይህችን ፡ ዓለም ፡ የሚገዙ ፤

በእንተ ፡ ግብረ ፡ እደዊሆሙ ፤

በእጃቸው ፡ በሠሩት ፡ ኃጢአት ፤ በቃላቸው ፡ በተናገሩት ፡ ክህደት ፡ የተዋረዱ ፡ ሆኑ ፡

እስመ ፡ በዕለተ ፡ ጻዕቆሙ ፡ ወጻሕቦሙ ፡ ኢያድኅኑ ፡ ነፍሶሙ ፡

በእጃቸው ፡ ስለሠሩት ፡ ክፉ ፡ ሥራቸው ፤ በዚያ ፡ ወራት ፡ እንገታቸውን ፡ የደፉ ፡ ሆኑ ፤ በተጨነቁባት ፡ ቀን ፡ ሰውነታቸውን ፡ አላዳኑምና ፤

፱ ፤ ወውስተ ፡ እደዊሆሙ ፡ ለኅሩያን ፡ ዚአየ ፡ ይወድዮሙ ፡ ውስተ ፡ እሳት ፤

በመረጥኋቸው ጻድቃን ፡ እጅ ፡ ሥሳሴ ፡ ይጥሏቸዋል ፡፡

፲ ፤ ከመ ፡ ሣዕር ፡ ውስተ ፡ እሳት ፤ ሣር ፡ በእሳት ፡ እንዲቃጠል ፡ በጻድቃን ፡ እጅ ፡ የሚጠፉ ፡ ሁነው ፡ አይደለም ፤ እርሱን ፡ በበደሉበት ፡ የሚፈረድባቸው ፡ ስለሆነ ፤

ወከመ ፡ ዓረር ፡ ውስተ ፡ ማይ ፤ እንደ ፡ እርሳስ ፡ በውሃ ፡ ውስጥ ፡ የሚሰጥም ፡ እንዲሰጥም ፤

ወከመዝ ፡ ይውዕዩ ፡ እምገጸ ፡ ጻድቃን ፡ ወይሰጠሙ ፡ እምቅድመ ፡ ገጸ ፡ ቅዱሳን ፤

አሁን ፡ እንደተናገርሁት ፡ ጻድቃን ፡ ከመበደላቸው ፡ የተነሣ ፡ በገሃነም ፡ ይቃጠላሉ ፤ ቅዱሳንን ፡ ከመበደላቸው ፡ የተነሣ ፡ በባሕረ ፡ ገሃነም ፡ ይሰጥማሉ ፡

፲፩ ፤ ወኢይትረከብ ፡ ሎሙ ፡ አሠር ፡ በዕለተ ፡ ጻሕበ ፡ ዚአሆሙ ፡ ፍርሀት ፡ ትከውን ፡ በዲበ ፡ ምድር ፤

በተጨነቁበትም ፡ ቀን ፡ ፍለጋቸው ፡ አይገኝም ፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ በሠሩት ፡ ኃጢአታቸው ፡ ፍርሀት ፡ ትደረጋለች ፤

፲፪ ፤ ወበቅድሜሁ ፡ ይወድቁ ፡ ወኢይትነሥኡ ፤

በፊቱም ፡ ይወድቃሉ ፡ አይነሡም ፤

ወአልቦ ፡ ዘይሜጥዎሙ ፡ እደዊሁ ፡ ወያነሥኦሙ ፤

ከክፉ ፡ ስፍራ ፡ ያለን ፡ ሰው ፡ አይዞህ ፡ አይዞህ ፡ እያሉ ፡ እን

ዲያወጡት ፡ ለማውጣት ፡እጁን፡ የሚሰጣቸው ፡ የለም ፤

እስመ ፡ ክህድዎ ፡ ለእግዚአ ፡ መና ፍስት ፡ ወለመሢሖ ፤

የመላእክት ፡ ጌታ ፡ አብን ፡ ክደ ውታልና ፡ የባሕርይ ፡ ልጁንም ክደዋልና ፤

ወይትባረክ ፡ ስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፤

በኃጥአን ፡ ፈርዶ ፡ ገሃነመ ፡ እሳትን ፣ ለጻድቃን ፡ ፈርዶ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያትን ፡ ባወረ ሰበት ፡ ጊዜ ፡ የመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስሙ ፡ ይመሰገናል ፤

፲፰ ፤ እስመ ፡ ጥበብ ፡ ተክዕወ ፡ ከመ ፡ ማይ ፤

ጥበቡ ፡ እንደ ፡ ውኃ ፡ በዝቶ ፡ ተሰጥቷልና ፤ እንድም ፡ የሕግ ዋጋዋ ፡ በዝቶ ፡ ተሰጥቷልና ፤ አንድም ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሀብቱ ፡ በዝቶ ፡ ተሰጥቷልና፤

ወስብሐት ፡ ኢተኀልቅ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤

ጌትነቱ ፡ ለዘለዓለም ፡ አትፈ ጸምም ፤

እስመ ፡ ኃያል ፡ ውእቱ ፡ በኵሉ ፡ ኅቡዓተ ፡ ጽድቅ ፤

የተሠወረውን ፡ ይገልጽ ፡ ዘንድ ከሀሊ ፡ ነውና ፣

፲፱ ፤ ወዓመፃ ፡ ከመ ፡ ጽላ ሎት ፡ የኀልፍ ፤

ኀጢአት ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ያል ፋል ፤ የጧት ፡ ጥላ ፡ በቀትር ፡ ጊዜ ፡ ከዚህ ፡ ደረሰ ፡ እንዳይባል ፣ እንዲጠፋ ፡ ኃጢአትም ፡ እንደዚያ፡ ያልፋል ፡ ይጠፋል ፤

ወምቅዋም ፡ አልቦ ፤

መቋሚያ ፡ የለውም ፤

እስመ ፡ ኅሩይ ፡ ቆመ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት፤

ኅሩይ ፡ ክርስቶስ ፡በመላእክት ፡ ጌታ ፡ በአብ ፡ ፊት ፡ ተቀምጧ ልና ፤

፳ ፤ ወስብሐቲሁ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤

ጌትነቱ ፡ ለዘለዓለም ፡ ነው ፤

ወኃይሉ ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ፤

ኃይሉም ፡ ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ዘመን ፡ ነው ፤

፳፩ ፤ ወቦቱ ፡ የኀድር ፡ መንፈስ ፡ ጥበብ ፤

የባሕርይ፡ጥበቡን፡ የሚገልጽበት መንፈስ ፡ ቅዱስ ፤ አንድም ፡ ለሌላው ፡ ጥበብን ፡ የሚገልጽበት፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በእርሱ ፡ ህልው ፡ ነው ፤

ወመንፈስ ፡ ዘያሌቡ ፤

አብ ፡የሚያውቀውን ፡ ዕውቀት የሚገልጽበት ፤ አንድም ፡ ለሌ ላው፡ዕውቀትን ፡የሚገልጽበት ፤

ወመንፈስ ፡ ትምህርት ፣

ወንጌልን ፡ የሚያስተምርበት ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፤ አንድም ፡ ለሌላው ፡ ትምህርትን ፡ የሚገ ልጽበት ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፣

ወኃይል ፤

ኃይል ፡ የሚያደርግበት ፤ አንድም ፡ ለሌላው ፡ ኃይል ፡ የሚያደርግ በት ፤

ወመንፈስ ፡ እሰ ፡ ኖሙ ፡ በጽድቅ ፤ በሃይማኖት ፡ አምነው ፡ የሞቱ ጻድቃንን ፡ የሚስያነሣ ፡ መንፈስ ቅዱስ ፡ በእርሱ ፡ ህልው ፡ ነው ፤

፳፪ ፤ ወውእቱ ፡ ይኴንን ፡ ዘኅቡ ዓት ፤

የተሰወረውን ፡ ኃጢአት ፡ መርምሮ ፡ ይፈርዳል ፤

ወነገረ ፡ በከ ፡ አልቦ ፡ ዘይክል ፡ ብሂለ ፡ በቅድሜሁ ፤

በፊቱ ፡ ዘበሬታ ፡ (ዋዛ ፡ ፈዛዛ) የሚናገር ፡ የለም ፤

እስመ ፡ ኅሩይ ፡ ውእቱ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡ በከመ ፡ ውእቱ ፈቀደ ፤

ኅሩይ ፡ ክርስቶስ ፡ በአብ ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡ ነውና ፤

፳፫ ፤ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ሚጠት ፡ ትከውን ፡ ለቅዱሳን ፡ ወለ ኅሩያን ፤

በዚያም ፡ ወራት ፡ ለደናግልና ፡ ለሕጋውያን ፡ መመለስ (ግዛት) ትደረግላቸዋለች ፡ ምላሽ ፡ ይሆናል ፤ ኃጥአን ፡ ከብረው ፡ ጻድቃን ፡ ተዋርደው ፡ ይኖሩ ፡ ነበር ፤ ዛሬ ፡ ግን ፡ ጻድቃን ፡ ከብረው ፡ ኃጥአን ፡ ተዋርደው ፡ ይኖራሉና ፤

ወብርሃነ ፡ መዋዕል ፡ ዲቤሆሙ የኅድር ፤

የዘመናት ፡ ብርሃን ፡ በጻድቃን ፡ ያድራል ፤ አንድም ፡ በዕለተ ፡ እሑድ ፡ የተገኘ ፡ ብርሃን ፡ ያድርባቸዋል ፤

ወስብሐት ፡ ወክብር ፡ ለቅዱሳን ፡ ይትመየጥ ፤

ፍጹም ፡ ጌትነትም ፡ ለቅዱሳን ይመለስላቸዋል ፤

፳፬ ፤ ወበዕለት ፡ እንተ ፡ ጻሕብ ፡ ትዘገብ ፡ እኪት ፡ ለኃጥአን ፤

በሚጨነቁባት ፡ ቀን ፡ ለኃጥአን ፡ መከራ ፡ ትደልባለች ፤

ወይመውኡ ፡ ጻድቃን ፡ በስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፤

በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስም ፡ ያመኑ ጻድቃንም ፡ ድል ፡ ይነሣሉ ፤

፳፭ ፤ ወያሬኢ ፡ ለካልዓን ፡ ከመ ፡ ይነስሑ ፡ ወይኅድጉ ፡ ምግባረ ፡ እደ ዊሆሙ ፤

ከጻድቃን ፡ ልዩ ፡ ለሚሆኑ ፡ ኃጥ አን ፡ ይመለሱ ፡ ዘንድ ፡ በእጃ ቸው ፡ የሠሩትን ፡ ኃጢአት ፡ በቃ ላቸው ፡ የሚናገሩትን ፡ ክህደት ፡ ይተዉ ፡ ዘንድ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሰው ፡ ሁኖ ፡ ያስረዳል ፤

፳፮ ፤ ወይከውን ፡ ሎሙ ፡ ክብር ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ወበ ስሙ ፡ ይድኅኑ ፤

በነፍሳት ፡ ጌታ ፡ ፊትም ፡ ክብር ፡ ይደረግላቸዋል ፤ በስሙም ፡ አም ነው ፡ ይድናሉ ፤

፳፯ ፤ ወእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ይም ሕሮሙ ፤

የነፍሳት ፡ ጌታ ፡ ይቅር ፡ ይላ ቸዋል ፤

እስመ ፡ ብዙኅ ፡ ምሕረቱ ፡ ወጻድቅ፡ ውእቱ ፡ በኰነኔሁ ፡ ወበቅድመ ፡ ስብሐቲሁ ፤

ቸርነቱ ፡ ብዙ ፡ ነውና ፡ በፍር ዱም ፡ በጌትነቱም ፡እውነተኛ ፡ ነውና ፤

፳፰ ፤ ወዓመባ ፡ ኢትቀውም ፡ በኰነኔሁ ፡ ወዘኢይኔስሕ ፡ በቅድሜሁ ይትኀጐል ፤

ሐሰት ፡ ነገርም ፡ በፍርዱ ፤ ጊዜ ፡ አትጸናም ፤ ኃጢአት ፡ ሠርቶ ፡ የማይመለስ ፡ ሁሉ ፡ ይጠፋል ፤

ወእምይእዜሰ ፡ ኢይምሕሮሙ ፡ ይቤ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤

የመላእክት ፡ ጌታም ፡ ንስሓ ፡ ያልገቡትን ፡ ሰዎች ፡ ይቅር ፡ አልላቸውም ፡ አለ ፤

፳፱ ፤ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ታገ ብዕ ፡ምድር ፡ማኅፀንታ ፤

በዚያም ፡ ወራት ፡ ምድር ፡ አደራዋን ፡ ትመልሳለች ፡ ሳይቀ ፁሩ ፡ የቀሩ ፡ እንደ ፡ ጸዳ ፡ እንደ ፡ ወግዳ ፡ እንደ ፡ ሳቢሳ ፡ በር ፤

ወሲኦልኒ ፡ ታገብእ ፡ ማኅጸንታ ፡ ዘተመጠወት ፤

ሲኦል ፡ መቃብርም ፡ የተቀበ ለችውን ፡ አደራ ፡ ትመልሳለች ፤

፴ ፤ ወኃጕል ፡ ያገብእ ፡ ዘይፈዲ ፤

ሞትም ፡ የሚከፍለውን ፡ ነፍስ ይመልሳል ፤

ወየኅሪ ፡ ጻድቃነ ፡ ወኄሩያነ ፡ እምኔ ሆሙ ፤

ከኃጥአን ፡ ጻድቃንን ፡ ይመር ጣል ፤

እስመ ፡ ቀርበት ፡ ዕለት ፡ ከመ እሙንቱ ፡ ይድኀኑ ፤

እነርሱ ፡ የሚድኑባት ፡ ቀን ፡ ቀርባለችና ፡

፴፩ ፤ ወኄሩይ ፡ በእማንቱ ፡ መዋዕል ዲበ ፡ መንበሩ ፡ ይነብር ፤

ለጻድቃን ፡ በሚፈርድበት ፡ በኃጥአን ፡ በሚፈርድበት ፡ ጊዜ ኄሩይ ፡ ክርስቶስ ፡ በዙፋኑ ይቀመጣል ፤

ወኵሉ ፡ ኅቡዓተ ፡ ጥበብ ፡ እምሕሊና፡ አፉሁ ፡ ይወጽእ ፤

በአንደበቱ ፡ ከሚነገረው ፡ ነገር የጥበብ ፡ ምሥጢር ፡ ይገኛል፤

እስመ ፡ እግዚእ ፡ መናፍስት ፡ ወሀቦ ወሰብሖ ፤

አብ ፡ ለወልድ ፡ የባሕርይ ፡ ክብ ሩን ፡ ገንዘብ ፡ አድርጎለታልና ፡ ጌትነቱንም ፡ ገልጾለታልና ፤

፴፪ ፤ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ይዘፍኑ አድባር ፡ ከመ ፡ ሐራጊት ፤

በእነዚያ ፡ ወራት ፡ ተራሮች ፡ እንደ ፡ ጊደር ፡ ይዘፍናሉ ፤ አለ ፤ በኃጥአን ፡ በሚፈርድባ ቸው ፤ ለጻድቃን ፡ በሚፈረድላ ቸው ፡ ጊዜ ፡ ነቢያት ፡ እንደ ፡ ጊደር ፡ ይዘላሉ ፤

ወአውግርኒ ፡ ያንፈርዕፁ ፡ ከመ መሐስዕ ፡ ጽጉባነ ፡ ሀሊብ ፤

ኮረብቶችም ፡ ወተት ፡ እንደጠ ገቡ ፡ ጠቦቶች ፡ ይዘላሉ ፡ አለ ፤ ደቂቀ ፡ ነቢያት ፡ ይዘላሉ ፤ አንድም፡ ሐዋርያት ፣ ሰብዓ ፡ አርድዕት ፡ ወተት ፡ እንደጠገቡ ፡ ጠቦቶች ፡ ይዘላሉ ፤

፴፫ ፤ ወይከውኑ ፡ ኵሎሙ ፡ መላእ ክተ ፡ በሰማይ ፤

ጻድቃን፡በሰማይ፡ ያሉ ፡ መላእክ ትን ፡ ይሆናሉ ፤ በሕይወት ፡ እንዲኖሩ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራሉ ፤ መላእክት ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ሲሉ ፡ እንዲኖሩ ፤ ቅዱስ፡ ቅዱስ ፡ ሲሉ ፡ ይኖራሉ ፤

ወገጾሙ ፡ ይበርህ ፡ በፍሥሐ ፤

ፊታቸውም ፡ በደስታ ፡ ይበራል፤

እስመ ፡ በእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ኀሩይ ተንሥአ ፤

በዚያ ፡ ወራት ፡ ኅሩይ ፡ ክርስቶስ ፡ በክፉው ፡ ሊፈርድበት ፣ ለበጎው ፡ ሊፈርድለት ፣ በጌትነቱ ፡ ተነሥቷ ልና ፤

፴፬ ፤ ወምድር ፡ ትትፌሣሕ ፤

መንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ያን ፡ ጊዜ ደስ ፡ ይላታል ፤ መግባታቸውን ፡ ደስታ ፡ አለመግባታቸውን ፡ ኀዘን ፡ አድርጎ ፡ ተናገረ ፤

ወጻድቃን ፡ ዲቤሃ ፡ የኃድሩ ፡ ወኅሩያን ፡ ውስቴታ ፡ የሐውሩ ወያንሶስዉ ፤

ጻድቃን ፡ በውስጧ ፡ ይኖራሉ ፡ ደናግልም ፡ በእሷ ፡ እየተመላለሱ፡ ይኖራሉ ።

## ምዕራፍ ፲፬
## ጉባኤ

፩ ፤ ወእምድኅረ ፡ እማንቱ ፡ መዋ ዕል ፡ በውእቱ ፡ መካን ፡ ኅበ ፡ ርኢኩ ፡ ኵሉ ፡ ራእያተ ፡ ኀቡዓተ ፤ ይህን ፡ ምሥጢር ፡ ካየሁበት ፡ ወራት ፡ በኋላ ፡ የተሠወረውን ፡ ራእይ ፡ ባየሁበት ፡ በዚህ ፡ ቦታ ፡ እስመ ፡ ተመሰጥኩ ፡ በነኵርኲረ ፡ ነፋስ ፤ በነፋስ፡ ሠረገላ ፡ ተነጥቄ ፡ ነበርና ፤ ወወሰዱኒ ፡ ውስተ ዓረብ ፤ በአራቱ ፡ መዓዝን ፡ አድርሰኛል ወስደኛልና ፤ አንድም ፡ መላእ ክት ፡ ወስደውኝ ፡ ነበርና ፤

፪ ፤ ወበህየ ፡ ርእያ ፡ አዕይንትየ ፡ ኀቡዓተ ፡ ሰማይ ፡ ኵሉ ፡ ዘይከውን፡ ሀሉ ፡ በዲበ ምድር ፤

በህየና ፡ በውእቱ ፡ መካን ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ነው ፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ይደረግ ፡ ዘንድ ፡ ያለው ፡ በሰማይ ፡ የተሠወረውን ፡ ምሥጢር ፡ ዓይ ኖቼ ፡ አዩ ፤

፫ ፤ ደብረ ፡ ሐፂን ፤

የብረት ፡ ተራራን ፤

ወደብረ ፡ ጸሪቅ ፤

የብርት ፡ ተራራን፤

ወደብረ ፡ ብሩር ፤

የብር ፡ ተራራን ፤

ወደብረ ፡ ወርቅ ፤

የወርቅ ፡ ተራራን ፤

ወደብረ ፡ ነጠብጣብ ፣

የዕይር ፡ (የናስ) ተራራን ፡
ወደብረ ፡ አረር፤
የእርሳስ ፡ ተራራን ፡ አዩ ፤ በዚህ ፡ ሁሉ ፡ የከበሩ ፡ ሰዎችን በየግብሩ ፡ ያሳየዋል ፤
፩ ፤ ወተስአልክዎ፡ ለመልአክ ፡ ዘየሐውር ፡ ምስሌየ ፡ እንዘ ፡ እብል ፡ ምንት ፡ እሙንቱ ፡ እሉ ፡ እለ ፡ በኅቡዕ ፡ ርኢኩ ፤
ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ ባልደረባዬ መልአኩንም ፡ ተሠውረው ፡ የማያቸው ፡ እኒህ ፡ ምንድን ፡ ናቸው ? ብዬ ፡ ጠየቅሁት ፤ ከእርሱ ፡ በቀር ፡ ያየው ፡ የለምና ፤ አንድም ፡ ሰዎችንም ፡ በወርቅ፡ በብር ፡ ተራራ ፡ እየመሰለ ፡ አሳይቶታልና ፤
፫ ፤ ወይቤለኒ ፡ እሉ ፡ ኵሎሙ ፡ ዘርኢከ ፡ ለሥልጣኑ ፡ መሲሑ ፡ እሙንቱ ፡ ይከውኑ ፡ ከመ ፡ የአዝዝ ወይትኃየል ፡ ዲበ ፡ ምድር ፤
እነዚያ ፡ ያየሀቸውን ፡ ሁሉ ፡ እንዲያዝ ፡ በዚህ ፡ ዓለምም ፡ እንዲበረታባቸው ፡ ልጁ ፡ በሥልጣኑ ፡ የሚፈርድባቸው ፡ ይሆናሉ፡ አለኝ ፤
፬ ፤ ወአውሥአኒ ፡ እንዘ ፡ ይብል፡ ውእቱ ፡ መልአክ ፡ ሰላም ፡ ጽናሕ ፡ ንስቲተ ፡ ወትሬኢ ፡ ወይትከሠት ፡ ለከ ፡ ኵሉ ፡ ዘኅቡዕ ፤
ከእኔም ፡ ከእግዚአብሔርም ፡ ጋራ ፡ ፍቅር ፡ አንድነት ፡ ያለው ፡ መልአክ፤እንዲህ ፡ አለኝ፤ጥቂት ፡ ቈይ ፡ ታያለህ ፤
ዘተከላ ፡ እግዚእ ፡ መናፍስት ፤
ዘአጽንዓ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ የመላእክት፡ ጌታ ፡ ያጸናው ፤ የተሠወረው ፡ ሁሉ ፡ ይገለጽልሃል ፡ ብሎ ፡ መለሰልኝ ።
፮ ፤ ወእሉንቱ ፡ አድባር ፡ ዘርኢከ ፡ ደብረ ፡ ሐፂን ፡ ወደብረ ፡ ጸሪቅ ፡ ወደብረ ፡ ብሩር ፡ ወደብረ ፡ ወርቅ ወደብረ ፡ ነጠብጣብ ፡ ወደብረ ፡ አረር፤
ያየሃቸው ፡ እነዚህም ፡ ተራሮች የብረቱ ፡ ተራራ ፤ የናሱም ፡ ተራራ ፤ የብሩም ፡ ተራራ ፤ የወርቁም ፡ ተራራ ፤ የዕይሩም ፡ ተራራ፤ የእርሳሱም ፡ ተራራ ፡ ይገለጽልሃል ፡ አለኝ ፤
እሉ ፡ ኵሎሙ ፡ ቅድሜሁ ፡ ለኅሩይ ይከውኑ ፡ ከመ ፡ መዓረ ፡ ግራ ፡ ዘቅድመ ፡ ገጸ ፡ እሳት ፤
እኒህ ፡ ሁሉ፡ በኅሩይ ፡ ክርስቶስ ፊት ፡ በእሳት ፡ ፊት ፡ እንዳለ ፡ እንደ ፡ ሰም ፡ እንደ ፡ አዶሮ ፡ ማር ፡ ይሆናሉ ፤ ይጠፋሉ ፡ አለ ፤
፯ ፤ ወከመ ፡ ማይ ፡ ዘይወርድ እምላዕሉ ፤
ከላይ ፡ የሚወርድ ፡ የመጣያ ውኃ ፡ ቀጥሎ ፡ ቀጥሎ ፡ እንዲወርድ ፤
ዲበ ፡ እማንቱ ፡ አድባር ፤
በሊህ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ መከራ ፡ ቀጥሎ ፡ ቀጥሎ ፡ መጥቶባቸዋል፤
ወይከውኑ ፡ ድኩማነ ፡ ታሕተ ፡ እገሪሁ ፤

ከእግሩ ፡ በታች ፡ የወደቁ ፡ ድኩ
ማን ፡ ይሆናሉ ፤
፱ ፤ ወይከውን ፡ በእማንቱ ፡ መዋ
ዕል ኢይድኅኑ ፡ ኢበወርቅ ፡ ወኢበ
ብሩር ፤
በእነዚያም ፡ ወራቶች ፡ እንደዚህ፡
ይሆናል ፤ ወርቅ ፡ ብርም ፡
ስጥተው ፡ ቢሆን ፡ አይድኑም ፡
ወኢይክሉ ፡ ድኂነ ፡ ወጕይየ ፤
ሸሽቶ፡ መዳን ፡ አይቻላቸውም፤
፲ ፤ ወኢይከውን ፡ ሐፂን ፡ ለፀብዕ፤
በዕለተ ፡ ሞት ፡ በዕለተ ፡ ምጽአት ፡
ብረት ፡ ጦር ፤ ጎራዴ ፡ ሁኖ ፡
አያድንም ፤
ወኢልብስ ፡ ለድርዓ ፡ እንግድኣ ፡
ልብስም ፡ ለደረት ፡ ጥሩር ፡
አይሆንም ፡ ኢይበቍዕ ፡ ብርት ፤
አንድም ፡ ለልብስ ፡ ሲል ፡ ነው ፤
ጽሩርም ፡ (ጥሩርም) ፡ ልብስ ፡
ሁኖ አያድንም ፤
ወኢናዕክ ፡ ኢይበቍዕ ፤
ዕይር ፡ ቅልቅል ፡ አያድንም ፤
ወኢይትኄለቍ ፤
ካለ ፡ ከሌለ ፡ አይቈጠርም ፤
ወዓረር ፡ ኢይትፌቀድ ፡ አላ ፡ ኵሎሙ ፡
ይትከሐዱ ፤
ዓረርም፡ በዕለተ ፡ ሞት ፡ አይ
ሻም ፡ አይፈለግም ፡ ሁሉም ፡
ይካዳሉ ፡ እንጂ ፤
፲፩ ፤ ወይትነሥሉ ፡ ሀለዎሙ ፡ እም
ገጸ ፡ ምድር ፡ ሶበ ፡ ያስተርኢ ፡
ኅሩይ ፡ በቅድመ ፡ ገጹ ፡ ለእግዚአ ፡
መናፍስት ፤

ኅሩይ ፡ ክርስቶስ ፡ በመላእክት
ጌታ ፡ በአብ ፡ ፊት ፡ በተገለጸ ፡
ጊዜ ፤ እሊህ ፡ ሁሉ ፡ ጠላቶቹ ፡
ኃጥአን ፡ በዕለተ ፡ ሞት ፤ በዕለተ ፡
ምጽአት ፡ ይጠፉ ፡ ዘንድ ፡ አላ
ቸው ፤
፲፪ ፤ ወበህየ ፡ ርእያ ፡ አእይንትየ
ቈላ ፡ ዕሙቀ ፡ ወርኅው ፡ አፉሁ ፤
ይህን ፡ ምሥጢር ፡ ባየሁ ፡
ጊዜ ፡ ጥልቅ ፡ ቈላን ፡ አየሁ ፡
አፉም ፡ የተከፈተ ፡ ነው ፤
መቃብርን ፡ አየሁ ፤
፲፫ ፤ ወኵሎሙ ፡ እለ ፡ የኃድሩ ፡
ዲበ ፡ የብስ ፡ ወባሕር ፡ ወደሰያት ፡
አምኃ ፤
በዚህ ፡ ዓለም ፤ በደሴትና ፡
በባሕርም ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡
እጅ ፡ መንሻ ፤
ወአስትዓ፤
ገጸ ፡ በረከት ፤
ወጋዳ ፡ ያመጽኡ ፡ ሎቱ ፤
ጊብር ፡ ያቀርባሉ ፤ ወንድሙን፤
እናቱን ፤ አባቱን ፡ የማይቀብር፡
የለምና ፤
ወዝክቱስ፡ ቈላ ፡ ዕሙቅ፡ ኢይመልዕ፤
ይህም ፡ ጥልቅ ፡ ቈላ ፡ አይሞ
ላም ፡ ማለት ፡ ሞት ፡ ቢገድል
መቃብር ፡ ቢቀበል ፤ በቃኝ ፡
አይልም ፤
፲፬ ፤ ወጌጋየ ፡ እደዊሆሙ ፡ ይገብሩ፤
እንዲህ ፡ ያለ ፡ ሞትና ፡ መቃ
ብር ፡ ሳለ ፡ እጃቸው ፡ ኃጢአ
ትን ፡ ይሠራል ፤

ወኵሉ ፡ ዘይዓምጺ ፡ ለጌጋይ ፡
ኃጥአን ፡ ይበልዑ ፤
ኃጥአን፡ኃጢአት ፡ ሊሆንባቸው፡
የደከሙበትን፡ኃጥአን ፡ ይበላሉ፤
እንድም ፡ ኃጥአን ፡ ኃጢአት፡
ሊሆንባቸው ፡ የደከሙበትን ፡
ጻድቃን ፡ ይበላሉ ፤ ዘዘገቡ ፡
ኃጥአን ፡ ይበልዑ ፡ ጻድቃን ፡
እንዲል[፩] ፡፡

፲፩ ፤ ወእምገጹ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍ
ስት ፡ ይትነገሉ ፡ ኃቅአን ፤
ከነፍሳት ፡ ጌታ ፡ ገጽ ፡ መዓ
ትም ፡ የተነሣ ፡ ኃጥአን ፡ ይጠ
ፋሉ ፤
ወእምገጸ ፡ ለምድረ ፡ ዚአሁ ፡ ይት
ቃወሙ ፤
ይትከልኡ ፡ሲል ፡ነው ፤ ከመ
ንግሥተ፡ሰማይም፡ ይከለከላሉ ፤

፲፮ ፤ ወኢየኀልቁ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤
ለዘለዓለሙ፡ፈርሰው ፡ በስብሰው
አይቀሩም፤
እስመ ፡ ርኢክዎሙ ፡ ለመላእክተ
መቅሠፍት ፡ እንዘ ፡ የሐውሩ ፤
መላእክተ፡መቅሠፍት፡አጋንንትን
ሲሄዱ ፡ አይቻቸዋለሁና ፤
ወያስተዴልዉ ፡ ኵሉ ፡ መባልዕተ ፡
ለሰይጣን ፤
ዙኃውን ፡ ጭፍጭፋን ፡ ሲያዘ
ጋጁ ፡ አየሁ ፤ መከራውን ፡ መና
ገር ፡ ነው ፤

፲፯ ፤ ወተስእልክዎ ፡ ለመልአክ ፡
ሰላም ፡ ዘየሐውር ፡ ምስሌየ ፡ ወእ
ቤሎ ፡ እሉንተ ፡ መባልዕተ ፡ ለመኑ ፡
ያስተዳልዉ ፤
ፍቅር ፡ ያለው ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡
የሚኖር ፡ መልአኩን ፡ እነዚህን
ዙኃዎች ፡ ለማን ፡ ያዘጋጇቸዋል?
ብዬ ፡ ጠየቅሁት ፤

፲፰ ፤ ወይቤለኒ ፡ እሉንተ ፡ ያስተዳ
ልዉ ፡ ለነገሥት ፡ ወለኃያላን ፡ ዘዝንቱ ፡
ምድር ፡ ከመ ፡ በቱ ፡ ይትኀጕሉ ፤
በእርሱ ፡ ይጠፉ ፡ ዘንድ ፡ ለዚህ ፡
ዓለም ፡ አርበኞችና ፡ ለነገሥታ
ቱም ፡ ያዘጋጃሉ ፡ አለኝ ፤

፲፱ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ ያስተርኢ
ጻድቅ ፡ ወኅሩይ ፡ ቤተ ፡ ምስት
ጉቡአ ፡ ዚአሁ ፤
ቤት ፡ ምስትጉቡእ ፡ አንድ ፡ ወገን፣
በማደሪያው ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይ፡
ኅሩይ ፡ ክርስቶስ ፡ ይገለጻል ፤
እንድም ፡ ማደሪያው ፡ በሆኑ ፡
ለጻድቃን ፡ ማደሪያ ፡ በሆነች ፡
በመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ይገለጻል ፤

፳ ፤ እምይእዜሰ ፡ ኢይትከልዑ ፡
በስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፤
በስሙ ፡ ያመኑ ፡ ጻድቃን ፡
ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ አይከለከሉም ፤

፳፩ ፤ ወእሉ ፡ አድባር ፡ ይከውኑ ፡
ቅድመ ፡ ገጹ ፡ ከመ ፡ ምድር፤
እኒህ ፡ ኃጥአን ፡ ምድር ፡ እንዲ
ረገጥ ፡ በፊቱ ፡ ይረገጣሉ ፤
ወየዐርፉ ፡ ጻድቃን ፡ እምዓማ ፡
ኃጥአን ፤

፩ ፤ እዮ. ፳፯፥፳፯ ፤

ኃጥአን ፡ ከሚያመጡባቸው ፡ መከራ ፤ አንድም ፡ ኃጥአን ፡ በነፍስ ፡ ከሚቀበሉት ፡ መከራ ፡ ያርፋሉ ፤

ይትዌጠን ፡ ሥላጤሃ ፡ ለነፍስ ፡ አሐቲ ፣ ተመጠነ ፡ ሞተ ፡ ሥጋ ፡ መዋቲ ፤

የአንዲት ፡ ነፍስ ፡ መካተቻ ፡ ይጀመር ፡ ዘንድ ፡ የኃላፊ ፡ ሥጋ ፡ ሞት ፡ ተሰናበተ ፡ ተለየ ፤

ወአውግር ፡ ይከውኑ ከመ ፡ ነቅዓ ማይ ፤

ጻድቃን ፡ እንደ ፡ ነቅዓ ፡ ማይ ፡ ይሆናሉ ፤ ክብራቸው ፡ ይበዛል ፤

፳፪ ፤ ወተመየጥኩ ፡ ወርኢኩ ፡ ካልዓ ፡ ገጸ ፡ ምድር ፤

ተመልሼም ፡ ሌላ ፡ ቦታ ፡ አየሁ ፤

ወሀየ ፡ ርኢኩ ፡ ቈላ ፡ ዕሙቀ ፤

ይህን ፡ ምሥጢር ፡ ባየሁ ፡ ጊዜ ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ገሃነምን ፡ አየሁ ፤

እንዘ ፡ ይነድድ ፡ እሳት ፤

ገሀነመ ፡ እሳት ፡ ሲነድበት ፡ አየሁ ፤

፳፫ ፤ ወእምጽእዎሙ ፡ ለነገሥት ፡ ወለኃያላን ፤

አርበኞቹንና ፡ ነገሥታቱን ፡ አምጥተው ፤

ወወደይዎሙ ፡ ውስተ ፡ ዝኩ ፡ ቈላ ዕሙቅ ፤

በዚያ ፡ በጥልቅ ፡ ቦታ ፡ ጣሏቸው ፤

፳፬ ፤ ወበህየ ፡ ርእያ ፡ አዕይንትየ ፡ ዘመባዕላቲሆሙ ፡ እንዘ ፡ ይገብርዎሙ ፡ ማዕሠርተ ፡ ሐፂን ፡ ዘአልቦ ፡ መድሉት ፤

በዚያ ፡ ቦታ ፡ ዓይኖቼ ፡ ዘኃዎችን ፡ ልክ ፡ መጠን ፡ በሌለው ፡ እግር ፡ ብረት ፡ ሰንሰለት ፡ ሲያስሯቸው ፡ አዩ ፤

፳፭ ፤ ወተስእልክዎ ፡ ለመልአክ ፡ ሰላም ፡ ዘየሐውር ፡ ምስሌየ ፡ እንዘ እብል ፡ እሉ ፡ ማዕሠራተ ፡ መባዕላት ለመኑ ፡ ይዴለዉ ፤

ከእኔ ፡ ጋራ ፡ የሚኖር ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋራ ፡ አንድነት ፡ ያለው ፡ መልአኩንም ፡ እነዚህ ፡ የዙኃዎች ፡ ማሠሪያዎችን ፡ ለማን ፡ ያዘጋጃሉ ፡ ብዬ ፡ ጠየቅሁት ፤

፳፮ ፤ ወይቤለኒ ፡ እሉ ፡ ይዴለዉ ፡ ለትዕይንተ ፡ አዛዝኤል ፡ ከመ ፡ ይመጥውዎሙ ፡ ወይደይዎሙ ፡ መትሕተ ፡ ኵሉ ፡ ደይን ፤

እሊህ ፡ እግር ፡ ብረት ፡ ሰንሰለት ፡ ለአዛዝኤል ፡ ሠራዊት ፡ ይዘጋጃሉ ፡ አለኝ ፣ በአዛዝኤል፡ ሠራዊት ፦ ከፍጥረት ፡ እስከ ፡ ምጽአት ፡ ያሉ ፡ ኃጥአንን ፡ መናገር ፡ ነው፤

፳፯ ፤ ወአዕባነ ፡ ጠዋያተ ፡ ይከድኑ ፡ መላትሒሆሙ ፡ በከመ ፡ አዘዘ ፡ እግዚአ፡ መናፍስት ፤

የመላእክት ፡ ጌታ ፡ እንዳዘዘ ፡ እንክብል ፡ እንክብል ፡ ደንጊያ ፡ በፊታቸው ፡ ይገጥሙባቸዋል ፡ የመከራውን ፡ ጽናት ፡ መናገር ነው ፤

፹፰ ፤ ሚካኤል ፡ ወገብርኤል ፡ ሩፋኤል፡ወፋኑኤል ፡ ውእቶሙ ፡ ያጸንዕ ምሙ ፡ በይእቲ ፡ዕለት ፡ ዓባይ ፤
ገብርኤልና ፡ ሚካኤል ፤ ሩፋኤልና ፡ ፋኑኤልም፡እነሱ ፡ ታላቅ በሆነች ፡ በዚያች ፡ ቀን ፡ አጽን ተው ፡ ይጣሏቸዋል ፤

፹፱ ፤ ወውስተ ፡ ዕቶነ ፡ እሳት ፡ ዘይነድድ ፡ ይወድይዎሙ ፡ ውእተ ፡ ዕለተ፡ ከመ ፡ ይትበቀል ፡ እምኔሆሙ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡'በዓመፃሆሙ ፤
የመላእክት ፡ ጌታ ፡ ከእነርሱ ፡ በቀልን ፡ ይመልስ ፡ ዘንድ ፡ በሠሩት ፡ ኃጢአት ፡ ከኃጥአን፡ ወገን ፡ ይበቀላቸው ፡ ዘንድ ፤
በእንተ ፡ ዘኮኑ ፡ ላእከ ፡ ለሰይጣን ፤
የሰይጣን ፡ ተገዥ ፡ ስለሆኑ ፤
ወአስሐትዎሙ ፡ ለእለ ፡ የኃድሩ ፡ ዲበ ፡ የብስ ፤
በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚኖሩትን ፡ ስለ ፡ አሳቱ ፡ ወደ ፡ ገሐነም ፡ ይጥሏቸዋል ፡ ይወድይዎሙ ፡ ላለው ፤

ጉባኤ

፺ ፤ ወበውእቱ ፡ መዋዕል ፡ ይወፅእ መቅሠፍቱ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፤
ደቂቀ ፡ ሴት ፡ ከደብር ፡ ቅዱስ በወረዱበት ፡ወራት ፡የእግዚአብሔር፡ መቅሠፍት ፡ የሚመጣበት ፡ ኃጢአት ፡ ይሠራል ፤ በግብሩ ፡መቅሠፍት ፡ ብሎታል፤

፺፩ ፤ ወይትረኀዉ ፡ ኵሎሙ ፡ መዛግብተ ፡ ማያት ፡ ዘመልዕልተ ፤ ሰማያት ፤
ከሰማያት ፡ በላይ ፡ ያሉ ፡ የውሃዎች ፡ በታዎች ፡ ሁሉ ፡ ይከፈታሉ ፡ አለ ፤ በደብር ፡ ቅዱስ ፤ በልዑል ፡ መዓርግ ፤ በሰማያዊ ፡ ግብር ፡ የሚኖሩ ፡ ደቂቀ ፡ ሴት ፡ የሚኖሩበት ፡ ደብር ፡ ቅዱስ ፡ ይገለጻል ፤
ወዲበ ፡ አንቅዕት ፡ እለ ፡ መትሕተ ፡ ሰማያት ፡ ወዘመልዕልተ ፡ ምድር ፤
ከሰማይ ፡ በታች ፡ ከምድር ፡ በላይም ፡ ያሉ ፡ የምንጭ ፡ በታዎች ፡ ሁሉ ፡ ይከፈታሉ ፡ አለ ፤ ከደብር ፡ ቅዱስ ፡በታች ፡ ባለ በምድረ ፡ ፋዩድ ፡የሚኖሩ፡ አዋልደ ፡ ቃየል ፡ ወደ ፡ ደቂቀ ሴት ፡ ይሄዳሉ ፤

፺፪ ፤ ወይዴመሩ ፡ ኵሎሙ ፡ ማያት ፡ ዘምስለ ፡ ማያት ፡ ዘመልዕልተ ፡ ሰማያት ፤
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያሉ ፡ ውሀዎች፡ ሁሉ ፡ ከሰማዮች ፡ በላይ ፡ካሉ ፡ ውሀዎች ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ይሆናሉ ፡ አለ ፤ አዋልደ ፡ ቃየል ፡ ከደብር ፡ ቅዱስ ፡ ከወረዱ ፡ከደቂቀ ፡ ሴት ጋራ ፡ በግብር ፡ አንድ ፡ ይሆናሉ ፤

፺፫ ፤ ማይሰ ፡ ዘመልዕልተ ፡ ሰማያት ፡ ተባዕታይ ፡ ውእቱ ፤
በሰማዮች ፡ በላይ ፡ ያለ ፡ ውሀ፡ ግን ፡ ተባዕታይ ፡ ነው ፡ አለ ፤ ከደብር ፡ ቅዱስ ፡ የወረዱት ፡ ወንዶች ፡ ናቸው ፤

ወማይሰ ፡ ዘመትሕተ ፡ ምድር ፡ አንስታይ ፡ ይእቲ ፤
በታች ፡ ያለችው ፡ ውሀም ፡ አን ስታይ ፡ ናት ፡ አለ ፤ ከደብር ፡ ቅዱስ ፡ በታች ፡ ካለ ከምድረ ፡ ፋዩድ ፡ የወጡት ፡ ሴቶች ፡ ናቸው ፤
፴፬ ፤ ወይደመስሱ ፡ ኵሉ ፡ እለ ፡ የጎድሩ ፡ ዲበ ፡ የብስ ፤ ወእለ ፡ የጎድሩ ፡ መትሕተ ፡ አጽናፈ ፡ ሰማይ ፤
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያሉና ፡ ከሰማይ ፡ ዳርቻ ፡ በታች ፡ የሚኖሩ ፡ ሁሉ ፡ ይደመሰሳሉ ፡ አለ ፤ ደቂቀ ፡ ሴት ፤ አዋልደ ፡ ቃየል በሥሩት ፡ ኃጢአት ፡ ይጠፋሉ ፤ አንድም ፡ ከአድማስ ፡ እስከ ፡ አድማስ ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ ይጠ ፋሉ ፤ አንድም ፡ ይወጽእ ፡ መቅ ሠፍቱ ፤ ደቂቀ ፡ ሴት ፡ አዋልደ ፡ ቃየል ፡ ኃጢአት ፡ በሠሩበት ፡ ወራት ፡ መቅሠፍቱ ፡ ማየ ፡ አይኅ ፡ ይመጣል ፤ ወይትረኀዉ ፡ ኵሎሙ ፡ መዛግብተ ፡ ማያት ፡ ዘመልዕተ ፡ ሰማያት ፤ ከጠፈር ፡ በላይ ፡ ያለ ፡ ሐኖስ ፡ ይከፈታል ፤ ከሰባት ፡ በታዎች ፡ ቀዶ ፡ አው ርዶታልና ፤ወዲበ ፡ አንቅዕት ፤ ከሰማይ ፡ በታች ፡ ወዳሉ ፡ አንቅዕት ፡ (ምንጮች) ፡ ይወር ዳሉ ፡ ወዘመትሕተ ፡ ምድር ፤ ከምድር ፡ በታች ፡ ይወጣሉ ፡ በሰባ ፤ አፈው (በታዎች) ቀዶ ፡ ከምድር ፡ አውጥቶታልና ፤ ወይ ዴመሩ ፤ ከምድር ፡ የነቁ ፡ ማያት ፡ ከሰማይ ፡ ከወረዱት ፡ ማያት ፡ ጋራ ፡ ይጨመራሉ ፤ ተባዕታይ ፡ ከሰማይ ፡ የወረደው ፡ ኃያል ፡ ነው ፤ ራስ ፡ ራስ ፡ የሚ ቀጠቅጥ ፡ ነው ፤ አንስትያ ፡ ከም ድር ፡ የሚመነጨው ፡ ድኩም ፡ ነው ፤ ደካማም ፡ ነው ፤ ፈል ፡ ፈል፡ የሚል ፡ ነው ፤ ወይደመስሱ ፡ እሊህ ፡ በሠሩት ፡ ኃጢአት ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ጽንፈ ፡ ዓለም፡ ጽንፍ ፡ እስከ ፡ ጽንፍ ፡ ያሉት ፡ ሁሉ ፡ በማየ ፡ አይኅ ፡ ይጠፋሉ ፤
፴፭ ፤ ወበእንተዝ ፡ አእምርዋ ፡ ለዓ መፃሆሙ ፡ እንተ ፡ ገብሩ ፡ በዲበ ምድር ፤
ይህ ፡ የሚመጣባቸው ፡ ስለሆነ የሠሯትን ፡ ኃጢአት ፡ በግብር አወቋት ፤ አንድም ፡ ይህ ፡ ስለ መጣባቸው ፡ የሠሯትን ፡ ኃጢ አት ፡ አወቋት ፤ ይህ ፡ ሁሉ ፡ የመጣብን ፡ በኃጢአታችን ፡ ነው ፡ አሉ ፤ አንድም ፡ አእመርዋኑ ፡ ይላል ፤ ይህ ፡ ስለ መጣባቸው ፡ የሠሯትን ፡ ኃጢአት ፡ አወቋትን ፤
ወበእንተዝ ፡ ይትኀጕሉ ፤ ዘአእመርዋ ፤ የሠሯትን ፡ ኃጢአት ፡ በግብር ፡ ስላወቋት ፡ ይደመሰሱ ፡ ላለው ፡፡

## ምዕራፍ ፲፭

፩ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ ነስሐ ፡ ርእሰ ፡ መዋዕል ፤
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ብሉየ ፡ መዋዕል ፡ ጌታ ፡ አዘነ ፤ ሰው ፡ አሁን ፡ ሲያውቅ ፡ ሥራውን ፡ ሠርቶ ፡ በሠራው ፡ ሥራ ፡ እንዲጸጸት ፤ ተጸጸተ ፡ ማለት ፡ አይደለም ፤ ለበጎ ፡ አብነት ፡ አድርጌ ፡ ብፈጥ ራቸው ፡ ለክፉ ፡ አብነት ፡ ሆኑ ፡ ብሎ ፡ ተጸጸተ ፤
ወይቤ ፡ በከ ፡ አኅጐልክዎሙ ፡ ለኩ ሎሙ ፡ እለ ፡ ይነብሩ ፡ ውስተ ፡ የብስ ፤
በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚኖሩትን ፡ ሰዎች ፡ በከንቱ ፡ ኃጢአታቸው አጠፋኋቸው ፤ አንድም ፡ ብላሽ ሁነው ፡ ሊቀሩ ፡ አጠፋኋቸው ፤
፪ ፤ ወመሐለ ፡ በስሙ ፡ ዓቢይ ፡ ከመ ፡ እምይእዜ ፡ ኢይገብር ፡ ከመዝ ፡ ለኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይነብሩ ዲበ ፡ የብስ ፤
ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ በዚህ ዓለም ፡ በሚ ኖሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ እንዲህ ፡ እንዳ ላደርግ ፡ ሕያውየ ብሎ ፡ ማለ ፤
፫ ፤ ወትእምርተ ፡ እወዲ ፡ በሰማይ ፡ ወይከውን ፡ ማዕከሌየ ፤
ቀስተ ፡ ደመናውን ፡ ምልክት ፡ አድርጌ ፡ በሰማይ ፡ አሳያለሁ ፤
ወማእከሌሆሙ ፡ ሃይማኖተ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፡ መጠነ ፡ መዋዕለ ፡ ሰማይ ዲበ ፡ ምድር ፤
በእኔና ፡ በእርሳቸው ፡ መካከል ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ የሰማይን ፡ ዘመን ፡ ያህል ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ መተማመኛ ፡ ይሆናል ፤
፬ ፤ ወእምዝ ፡ በትእዛዝየ ፡ ውእቱ ፡ ሶበ ፡ ፈቀድኩ ፡ ከመ ፡ አጽንዖሙ ፡ በእደ ፡ መላእክት ፤
አጽንቼ ፡ በትእዛዜ ፡ ልጣላቸው ብወድ ፡ በእደ ፡ መላእክት ፡ ነው ፤ አንድም ፡ በእደ ፡ መላእክትም አጽንቼ ፡ ነው ፤ ልጣላቸው ፡ ብወድ ፡ በትእዛዜ ፡ ነው ፤
፭ ፤ በዕለተ ፡ ምንዳቤ ፡ ወሕማም ፡ ፍጹም ፡ መከራ ፡ በሚቀበሉበት ቀን ፡ በእደ ፡ መላእክት ፡ ነው ፤
እምቅድመዝ ፡ መዓትየ ፡ ወመቅሠፍ ትየ ፡ የኀድር ፡ ላዕሌሆሙ ፤
ተቈጥቼ ፡ በእደ ፡ መላእክት ፡ ከማመጣው ፡ መቅሠፍት ፡ አስቀ ድሞ ፡ በቃል ፡ አመጣለሁ ፤ መዓቴ ፡ መቅሠፍቴ ፡ ማየ ፡ አይኅ ፡ ታድርባቸዋለች ፤ አንድም ፡ እም ቅድመዝ ፡ ባለው ፡ ቁሞ ፡ ከመ ዓቴ ፤ ከመቅሠፍቴ ፡ አስቀድሞ ፡ መዓቴ ፤ መቅሠፍቴ ፡ ታድርባ ቸዋለች ፤ አንድም ፡ መልቶ ፡ ይጽፏል ፤ እምቅድመዝ ፡ መዓ ትየ ፡ ወመቅሠፍትየ ፡ ተኀድር ፡ ላዕሌሆሙ ፡ መዓትየ ፡ ወመቅሠ

ፍትየ ፡ ይላል ፤ እንደ ንባቡ ፡ ተርጕም ፤

፮ ፤ ይቤ ፡ እግዚአብሔር ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ነገሥት ፡ ኃያላን ፡ እለ ፡ ተኀድሩ ፡ ዲበ ፡ የብስ ፡ ሀለወክሙ ፡ ትርአይዎ ፡ ለኅሩየ ፡ ዚአየ ፡ አመ ፡ ይነብር ፡ በመንበረ ፡ ስብሐቲሁ ፤

የመላእክት ፡ ጌታ ፡ እግዚአብሔርም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የምትኖሩ ፡ ኃይለኞች ፡ ነገሥት ፡ የመረጥሁት ፡ ልጄን ፡ በጌትነቱ ፡ ዙፋን ፡ በተቀመጠ ፡ ጊዜ ፡ ታዩት ፡ ዘንድ ፡ አላችሁ ፡ አለ ፤

፯ ፤ ወይኬንኖ ፡ ለአዛዝኤል ፡ ወለኵሎሙ ፡ ማኅበረ ፡ ዚአሁ ፡ ወለኵሎሙ ፡ ትዕይንተ ፡ ዚአሁ ፡ በስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፤

በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ስም ፡ ያላመኑ ፤ አንድም ፡ በስሙ ፡ ያላመኑትን ፡ ይፈርድባቸዋል ፤

፰ -፤ ወርኢኩ ፡ በህየ ፡ ትዕይንተ ፡ መላእክት ፡ ዘመቅሠፍት ፤

ይህን ፡ ምሥጢር ፡ ባየሁበት ፡ ቦታ ፡ የመላእክተ ፡ መቅሠፍትን ከተማ ፡ አየሁ ፤

እንዘ ፡ የሐውሩ ፤

ኃጥአንን ፡ ለመቄራኘት ፡ ሲሄዱ ወእትኀዛን ፡ መሣግረ ፡ ሐፂን ፡ ወብርት ፤

የብርት ፡ የብረት ፡ እግር ፡ ብረት ፡ ሰንሰለት ፡ ይዘዋል ፤

፱ ፤ ወተስእልክዎ ፡ ለመልአከ ፡ ሰላም ፡ ዘየሐውር ፡ ምስሌየ ፡ እንዘ ፡ እብል ፡ ለመኑ ፡ የሐውሩ ፡ እለ ፡ ይእኀዙ ፤

ከእኔ ፡ ጋር ፡ የሚኖር ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋራ ፡ አንድነት ፡ ያለው ፡ መልአኩን ፡ እግር ፡ ብረቱን ፤ ሰንሰለቱን ፡ የያዙ ፡ እነዚህ ፡ ማንን ፡ ሊያስሩ ፡ ይሔዳሉ ፡ ብዬ ፡ ጠየቅሁት ፤

፲ ፤ ወይቤለኒ ፡ ፩ዱ ፡ ፩ዱ ፡ ለኅሩያኒሁ ፡ ዚአሆሙ ፡ ወለፍቁራኒሁ ፡ ዚአሆሙ ፤

ከአጋንንት ፡ አንዱም ፡ አንዱ ፡ አጋንንትን ፡ የወደዱ ፤ አጋንንትን ፡ የመረጡ ፡ ኃጥአንን ፡ ይቄራኙ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤ አንድም ፡ አጋንንት ፡ የወዳጃቸው ፤ አጋንንት ፡ የመረጧቸው ፡ ኃጥአንን ፡ ይቄራኙ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤ ሐተታ ፡ መጀመሪያው ፡ ኃጢአት ፡ ጣዖት ፤ ማምለክ ፤ አጋንንትን ፡ መውደድ ፡ ነውና ፤

ከመ ፡ ይትወደዩ ፡ ውስተ ፡ ንቅዓተ ፡ ማዕምቅ ፡ ዘቈላ ፤

በቈላ ፡ ባለ ፡ በጥልቅ ፡ ገደል ፡ ይወድቁ ፡ ዘንድ ፤ አንድም ፡ በገሃነም ፡ ባለ ፡ በጽኑ ፡ መከራ ይጠፉ ፡ ዘንድ ፤

፲፩ ፤ ወእሚሃ ፡ ይመልዕ ፡ ውእቱ ፡ ቈላ ፡ እምኀ ፡ ኅሩያን ፡ ወፍቁራኒሁ ፡ ዚአሆሙ ፤

ኅሩያኒ ፡ ዚአሆሙ ፡ ፍቁራኒ ፡ ዚአሆሙ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ እላቸውን ፡ ከወደዱ ፤ እላቸውን ፡

ከመረጡ ፡ ከኃጥአን ፡ የተነሣ ፤
እንድም፡ እሳቸው፡ ከወደዷቸው
ከመረጧቸው ፡ ከኃጥአን ፡ የተ
ነሣ ፡ ገሃነም ፡ ይመላል ፤
፲፪ ፤ ወይትዌዳዕ ፡ ዕለተ ፡ ሕይወ
ቶሙ ፡ ወዕለተ ፡ ስሕተቶሙ ፤
የሚስቱበት ፤ የሚያስቱበት ፡
በሕይወት ፡ የሚኖሩበት ፡ ቀን
ይፈጸማል ፤
እምይእዜ ፡ ኢይትኌለቍ ፤
ከወረዱ ፡ ጀምሮ ፡ካሉ ፡ ከሌሉ
አይቈጠሩም ፤
፲፫ ፤ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ይትጋ
ብኡ ፡ መላእክት ፤
መላእክት ፡ በሚጠፉበት ፡ ወራት ፡
እለ ፡ ሆሴዕ ፡ ወልደ፡ ኤላ ፤ እለ ፡
ፋቁሔ ፡ ወልደ ፡ ሮሜልዩ ፡
ኃጢአት ፡ ለመሥራት ፤ ጣዖት ፡
ለማምለክ ፡ ይሰበሰባሉ ፤
ወይወድዩ፡አርእስቲሆሙ፡ ለምሥራቅ፡
ለገበ ፡ ሰብእ ፡ ጳርቴ ፡ ወሜድ ፤
የፋርስን ፤ የሜዶንን ፡ ሰዎች ፡
ለማምጣት ፡ ራሳቸውን ፡ ወደ ፡
ምሥራቅ ፡ ይመልሳሉ ፤
፲፬ ፤ ወየሐውስዎሙ፡ ለነገሥት ፤
እለ ፡ ስልምናሶርን ፡ ያናውጧ
ቸዋል ፤
ወይበውእ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ መንፈሰ ፡
ሐውክ ፤
በእለ ፡ ሆሴዕ ፡ ወልደ ፡ ኤላ ፡
ሁከት ፡ የያዘ ፡ ልቡና ፡ ያድርባ
ቸዋል ፤ ኃጢአት ፡ ሥሩ፤ ጣዖት ፡
አምልኩ ፡ የሚል ፡ ነው፤

ወየሐውክዎሙ ፡ እመናብርቲሆሙ ፤
እለ፡ ስልምናሶርን ፡ ከዙፋናቸው
ያወርዷቸው ፡ ዘንድ ፡ ያውኳቸ
ዋል ፤ ኃጢአት ፡ መሥራት ፤
ጣዖት ፡ ማምለክ ፤ ማርኩን ፡
ማለት ፡ ነውና ፤ እንድም ፡
እስራኤል ፡ ኃጢአት ፡ በሠሩበት ፤
ጣዖት ፡ ባመለኩበት ፡ ወራት ፡
ይትጋብኡ ፡ እስራኤልን ፡ ለመ
ማረክ ፡ እለስልምናሶር ፡ ይሰበ
ሰባሉ ፤ ወይወድዩ ፡ የፋርስ
የሜዶንን ፡ ጦር ፡ ለመሰብሰብ ፡
ፊታቸውን፡ ወደምሥራቅ፡ ይመ
ልሳሉ ፤ የሐውስዎሙ ፤ ድንገት ፡
ሳያስቡት ፡ አርዱን ፡ ብለው ፡
ያናውጧቸዋል ፤ እንድም ፡ እለሆ
ሴዕን ፡ ይማርኳቸዋል ፤ መንፈሰ ፡
ሐውክ ፤ በእለስልምናሶር ፡
እስራኤልን ፡ ውጋ ፡ ውጋ ፡
የሚል ፡ የሁከት ፡ ልቡና ፡ ያድ
ርባቸዋል ፤
ወየሐውክዎሙ ፤ አርዱን፡ ብለው፡
ድንገት ፡ ሳያስቡት ፡ከዙፋናቸው፡
ያወርዷቸዋል ፤ እንድም ፡ እለ
ሆሴዕን ፡ ይማርኳቸዋል ፡
፲፭ ፤ ወይወፅኡ ፡ ከመ ፡ አናብስት ፡
እምስካባቲሆሙ ፡ ወከመ ፡ አዝእብት፡
ርኁባን ፡ ማዕከለ ፡ መርዔተ ፡ ዚአ
ሆሙ ፤
እለስልምናሶር ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡
እንደ ፡ ተራብ ፡ ጅብ ፡ በማስፈ
ራት ፡ ይወጣሉ ፤
፲፮ ፤ ወየዐርጉ ፤
ወደ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ይዘምታሉ ፤

ወይከይድዋ ፡ ለምድረ ፡ ኅሩያን ፡
ዚአሆሙ ፤
ለመማረክ ፡ የመረጧቸው ፡ የእ
ስራኤልን ፡ ሀገር ፤ አንድም ፡
እርሳቸውን ፡ የመረጡ ፡ የእስራ
ኤልን ፡ ሀገር ፡ ኅሩያን ፡ ዚአሁ ፡
ቢል ፡ እግዚአብሔር ፡ የመረጣ
ቸው ፡ የእስራኤልን ፡ ሀገር ፡ እለ
ስልምናሶር ፡ ይረግጡታል ፤
ምድረ ፡ ኅሩያን ፡ ዚአሁ ፡ በቅድ
ሜሆሙ ፡ ምክያደ ፡ ወአሠረ ፤
እግዚአብሔር ፡ የመረጣቸው ፡
ዚአሆሙ ፡ ቢል ፡ አሕዛብ ፡ ለመ
ማረክ ፡ የመረጧቸው ፡ የእስራ
ኤል ፡ ምድር ፤ አንድም ፡ እሳቸ
ውን ፡ የመረጡ ፡ የእስራኤልን ፡
ምድር ፡ መገሳገሻ ፡ ያደርጓታል ፤
፲፯ ፤ ወሀገረ ፡ ጻድቃን ፡ ዚአየ ፡
ይከውን ፡ ማዕቅፈ ፡ ለአፍራሲሆሙ ፤
የወዳጆቼ ፡ የሁለቱ ፡ ነገድ ፡
ሀገር ፡ ለፈረሶቻቸው ፡ መሰና
ክል ፡ ትሆናለች ፤
፲፰ ፤ ወያነሥኡ ፡ ቀትለ ፡ በበይና
ቲሆሙ ፤
ዐሥሩ ፡ ነገድ ፡ እርስ ፡ በር
ሳቸው ፡ ይዋጋሉ ፡ የአንዱን ፡
ገንዘብ ፡ አንዱ ፤ ይበላዋል ፤
ኤፍሬም ፡ ይበልዖ ፡ ለምናሴ ፡
ወምናሴ ፡ ይበልዖ ፡ ለኤፍሬም ፡
[፩]እንዲል ፡
ወትጸንዕ ፡ የማኖሙ ፡ ዲቤሆሙ ፤
የወንድሞቻቸው ፡ ሥልጣን ፡
በወንድሞቻቸው ፡ ላይ ፤ አንድም
የአሕዛብ ፡ ሥልጣን ፡ በእስራ
ኤል ፡ ላይ ፡ ትጸናለች ፤
ወኢየአምሮ ፡ ብእሲ ፡ ለካልዑ ፡ ወለ
እኁሁ ፤
ወዳጅ ፡ ወዳጁን ፡ ወንድም ፡
ወንድሙን ፡
፲፱ ፤ ወኢወልድ ፡ ለአቡሁ ፡ ወለእሙ ፤
ልጅ ፡ እናቱን ፤ አባቱን ፡ በፍ
ቅር ፡ አያውቅም ፤ አንድም ፡
እናት ፡ አባት ፡ ልጃቸውን ፡ በፍ
ቅር ፡ አያውቁም ።
እስከ ፡ ይከውን ፡ ኍልቈ ፡ አብድንቲ
ሆሙ ፡ እሞቶሙ ፡ ወእመቅሠፍቶሙ ፡
ወኢይከውን ፡ በከ ፤
እስከ ፡ ያለውን ፡ አመጣው ፤
በከ ፡ እስከማይሆን ፡ ድረስ ፡
የሚቆጠር ፡ የሬሳቸው ፡ ቍጥር
እንዲህ ፡ እስኪሆን ፡ ድረስ ፡ ባለ ፡
አለንጋው ፡ ባለ ፡ ሽፋፋው ፡
ይህን ፡ ያህል ፡ ተብሎ ፡ እስኪቆ
ጠር ፡ ድረስ ፤ እስከ ፡ ኢይከውን ፡
ቢል ፡ የማይቈጠር ፡ እስኪሆን ፡
ድረስ ፤
፳ ፤ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ትፈ
ትሕ ፡ አፋሃ ፡ሲኦል ፤
እስራኤል ፡ በሚማረኩበት ፡
ወራት ፡ ፋርስ ፡ አፏን ፡ ትከፍታ
ለች ፡ ታላቅቃለች ፤ ትውጣቸ
ዋለች ፤
፳፩ ፤ ወይሠጠሙ ፡ ውስቴታ ፡
ውኅጕሎሙ ፡ ሲኦል ፡ ትውኅጦሙ ፡
ለኃጥአን ፡ እምቅድመ ፡ ገጸ ፡ ኅሩያን ፤
ነቢያት ፡ ካህናትን ፡ ከመበደ
ላቸው ፡ የተነሣ ፡ ኃጕሎሙ ፡

፩ ፤ ኢሳ. ፱፥፳

ፋርስ ፡ ትውጣቸዋለች ፤ አን ድም ፡ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፤ እለ ፡ ብልጣሶር፡ኃጢአት ፡ በሚ ሠሩበት ፣ ጣዖት ፡ በሚያመል ኩበት ፡ ወራት ፡ ይሰበሰባሉ ፤ አንድም ፡ ወይወድዩ ፤ የፋርስ፡ የሚዶንን ሰዎች ፡ ለማምጣት ፡ ፊታቸውን ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ይመልሳሉ ፤ የሐውስምሙ ፤ ነገሥታቱን ፡ ኑ ፡ ማርኩን ፡ ብለው፡ ያነዋውጧቸዋል ፤ ኃጢ አት ፡ መሥራት ፣ ጣዖት ፡ ማምለክ ፡ ማርኩን ፡ ማለት ፡ ነውና ፤ መንፈስ ፡ ሀውክ ፤ በእለብልጣሶር ፡ ልቡና ፡ ኃጢ አት ፡ ሥሩ ፡ የሚል ፡ ሁከት ፡ ያለበት ፡ ልቡና፡ያድርባቸዋል ፤

ወየሀውክምሙ ፤

ነገሥታቱን ፡ ማርኩን ፡ ብለው፡ ያውኳቸዋል ፤ኃጢአት ፡ መሥ ራት ፣ ጣዖት ፡ ማምለክ ፣ ማር ኩን ፡ ማለት ፡ ነውና ፤ አንድም፡ የባቢሎን ፡ ሰዎች ፡ በሚጠፉ በት ፡ እስራኤልን ፡ በበደሉበት፡ ወራት ፡ እለቂሮስ ፡ እለ፡ ዳር ዮስ ፡ ይሰባሰባሉ ፤ወይወድዩ ፣ የፋርስን ፡ የሚዶንን ፡ ጦር ፡ ለመ ሰብሰብ ፡ ፊታቸውን ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ይመልሳሉ ፤ ወየሐው ስምሙ ፤ ያነዋውጧቸዋል ፤ ያለ ፡ ፈቃዳቸው ፡ እርዱን ፡ ብለው ፤ አንድም ፡ እለ ፡ ብልጣሶር ፡ ያነ ዋውጧቸዋል ፡በሞት፣ መንፈስ፡ ሀውክ ፤ ውጋ ፡ ውጋ ፡ የሚል፡ የሁከት፡ ልቡና ፡ ያድርባቸዋል፤ ወየሀውክምሙ ፤ ያለ ፡ ልባቸው ፡ እርዱን ፡ ብለው ፡ ያውኳቸዋል ፤ አንድም ፡ እለብልጣሶርን ፡ በሞት ፡ ያነዋውጧቸዋል ፤ ከመ ፡ አንበሳ ፡ ወከመ ፡ አዝእብት ፣ እለ ፡ ቂሮስ ፡ እለ ፡ ዳርዮስ ፡ እንደ ፡ ተራብ ፡ ጅብ ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ በማስፈራት ፡ ይመጣሉ ፤ ወየዐርጉ ፣ ወደፋርስ ፡ ይዘምታሉ ፣ ወይከይድዋ ፡ ለም ድር ፣ እሳቸውን ፡ የመረጡ ፡ የባቢሎን ፡ ምድር ፤ አንድም ፡ እሳቸው ፡ የመረጧቸው ፡ የባቢ ሎንን ፡ ምድር ፤ አንድም ፡ ኅሩያን ፡ ዚአሁ ፡ ቢል ፣ ጌታ ፡ ሰባ ፡ ዘመን ፡ መርጧቸው ፡ የነበሩ ፡ የባቢሎንን ፡ ምድር ፡ እለቂሮስ ፡ እለዳርዮስ ፡ ይረግጧ ታል ፤ ምክያደ ፣ የእነቂሮስ ፡ የእነዳርዮስ ፡ መገሳገሻ ፡ ትሆና ለች ፤ ወሀገረ ፡ ጻድቃን ፡ ዚአየ ፣ የትሩፋን ፡ ሀገር ፡ ለፈረሶቻቸው ፡ መሰናክል ፡ ትሆናለች ፤ ወያነ ሥኡ ፡ ቀትለ ፣ የባቢሎን ፡ ሰዎች ፡ እርስ በርሳቸው ፡ ይዋ ጋሉ ፤ አንድም ፡ የባቢሎንና ፡ የፋርስ ፡ ሰዎች ፡ ይዋጋሉ ፤ ሌላውን ፡ አንድ ፡ ሆነው ፡ ይወጉ ፡ ነበረና ፡ በበይናቲሆሙ ፡ እለ ፤ ወትጸንዕ ፣ የባቢሎን ፡ ሰዎች ፡ ያንዱ ፡ ሥልጣን ፡

ባንዱ ፡ ላይ ፡ ትጸናለች ፤ (ትሆ
ናለች)፤ እንድም ፡ የፋርስ ፡
ሥልጣን ፡ በባቢሎን ፡ ሰዎች ፡
ላይ ፡ ትጸናለች ፤ ወኢየአምሮ፤
ከባቢሎን ፡ ሰዎች ፡ ወንድም ፡
ወንድሙን ፡ በፍቅር ፡ አያውቀ
ውም ፤ ወኢይከውን ፡ በከ ፤
የማይቆጠር ፡ እስከማይሆን ፡
ድረስ ፤ እንድም ፡ ወይከውን ፤
ቢል ፤ የሚቆጠር ፡ እስኪሆን ፡
ድረስ ፤ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል፡
ትፈትሕ ፡ አፉሃ ፤ እስራኤል ፡
በጠፋበት ፡ ወራት ፡ መቃብር ፡
አፏን፡ትከፍታለች ፤ ወኃጉሎሙ፤
ኀጉላቸው ፡ መቃብር ፡ ትውጣ
ቸዋለች ፤ እምገጸ ፡ ኅሩያን ፤
እስራኤል ፡ ትሩፋንን ፡ ከመበደ
ላቸው ፡ የተነሣ ፤

፷፱ ፤ ወኮነ ፡ እምድኅረዝ ፡ ርኢኩ ፡
ካልአ ፡ ትዕይንተ ፡ ሠረገላት ፤
የሠረገላውን ፡ ከተማ ፤ እንድም
ብዙ ፡ ሠረገላ ፡ እየሁ ፤
እንዘ ፡ ይጼዓኑ ፡ ሰብእ ፡ ዲቤሆሙ፤
በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ተቀምጠው ፤
እየሁ ፤ እንድም ፡ ያልታወቁ ፡
አሕዛብ ፤ እለሰናክሬም ፡ እለሐ
ሳዊ ፡ መሢሕ ፡ ናቸው ፤

፷፫ ፤ ወይመጽኡ ፡ ዲበ ፡ ነፋሳት ፡
እምሥራቅ ፡ ወእምዕራብ ፡ እስከ ፡
መንፈቀ ፡ ዕለት ፤
በነፋሶችም ፡ ላይ ፡ ተጭነው ፡
ከምዕራብና ፡ ከምሥራቅ ፡ እስከ
እኩለ ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ ይመ
ጣሉ ፤ ማለት ፡ ነፋስ፡- ፈጣን፡
ነው ፤ ፈጥነው ፡ ይመጣሉ ፤

፷፬ ፤ ወተሰምዐ ፡ ድምፀ ፡ ሠረገ
ላቲሆሙ ፤
የመዝመታቸው፡ድምጽ፡ተሰማ፤
ወሰበ ፡ ኮነ ፡ ዝ ፡ ሀውከ ቅዱሳን ፡
እምሰማይ ፡ አእመሩ ፤
ያልታወቁ፡ አሕዛብ ፤ እንድም ፡
እለ ፡ ሰናክሬም፡ የእለ ፡ ሐሳዊ፡
መሢሕ ፡ ጥፋት ፡ በተሰማ ፡
ጊዜ ፡ በሰማይ ፡ ቅዱሳን ፡ መላእ
ክት፡ አወቁ ፤

፷፭ ፤ ወዓምደ ፡ ምድር ፡ ተሐውሰ ፡
እመንበሩ ፤
ንጉሥ ፡ ምድር ፡ ጠፋ ፡ አለ ፡
ያልታወቁ ፡ አሕዛብ ፤ እንድም ፡
እለ ፡ ሰናክሬም ፡ እለ ፡ ሐሳዊ
መሢሕ ፡ ጥፋትን ፡ ጠፋ ፤

፷፮ ፤ ወተሰምዐ ፡ እምአጽናፈ ፡
ምድር ፡ እስከ ፡ አጽናፈ ፡ ሰማይ ፡
በአሐቲ ፡ ዕለት ፤
ጥፋቱም ፡ ከሰማይ ፡ ዳርቻ ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ
ድረስ ፡በአንዲት፡ ቀን ፡ተሰማ፤

፷፯ ፤ ወይወድቁ ፡ ኵሎሙ ፡ ወይሰ
ግዱ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፤
ባልታወቁ ፡ አሕዛብ ፡ ጥፋት ፡
ያልታወቁ፡ አሕዛብ ፤ በእለሰናክ
ሬም፡ጥፋት፡እስራኤል ፤ በእለ ፡
ሐሳዊ ፡ መሢሕ ፡ ምዕመናን ፤
ለመላእክት ፡ጌታ ፡ ይሰግዳሉ ፤

፳፰ ፡ ወዝንቱ : ውእቱ : ተፍጻሜተ : ካልእ : ምሳሌ ፡

የሁለተኛው : ነገር : መጨረሻ ይህ : ነው ፡

፳፱ ፡ ወአኀዝኩ : እብል : ሣልሰ : ምሳሌ : በእንተ : ጻድቃን : ወበእንተ ኅሩያን ፤

የሕጋውያንን : የደናግልን : ነገር : ሦስተኛ : ነገር : እናገር : ዘንድ : ጀመርሁ ፡

፴ ፡ ብፁዓን : አንትሙ : ጻድቃን : ወኅሩያን : እስመ : ስቡሕ : ክፍል ክሙ ፡

ዕድላችሁ : መንግሥተ : ሰማያት የበራ ፤ የተመሰገነ ፤ ነውና ፡

እናንተ : ጻድቃን : የተመረጣ ችሁ : የተደነቃችሁ : ናችሁ ፡

፴፩ ፡ ወይከውኑ : ጻድቃን : በብር ሃነ : ፀሐይ ፡

ሕጋውያን : ከክርስቶስ : በሚያ ገኙት : ብርሃን : ያበራሉ ፡

ወኅሩያን : በብርሃነ : ሕይወት : ዘለዓለም ፡

ደናግልም : ከመንፈስ : ቅዱስ : ባገኙት : ብርሃን : ያበራሉ ፡

ማካፈል : አይደለም ፡

፴፪ ፡ ወማኅለቅት : አልቦቱ : ለመዋዕለ : ሕይወቶሙ ፡ ወለቅዱሳን : ኍልቈ : መዋዕል : አልበሙ ፤

በሕይወት : ለሚኖሩ : አነዋወር : ፍጻሜ : የለውም ፤ በቅዱ ሳንም : የተቈጠረ : ዘመን : የላ ቸውም ፡

፴፫ ፡ ወየኀሥሥዎ : ለብርሃን ፡

ከክርስቶስ : የሚያገኙትን : ዕው ቀት : ይፈልጋሉ ፡

ወይረክቡ : ጽድቀ : በኀበ : እግዚእ : መናፍስት ፣

በመላእክት : ጌታም : ዘንድ : ጸጋውን : ክብሩን : ያገኛሉ ፡

፴፬ ፡ ወሰላም : ለጻድቃን : ይከውን : በኀበ : እግዚእ : መናፍስት ፡

ይህን : ዓለም : ከሚገዛ : ከሚያ ሳልፍ : አዙሮ : ካሳየኝ : ከመ ላእክት : ጌታ : ዘንድ : ፍቅር : አንድነት : ጸጋ : ክብር : አላቸው ፡

፴፭ ፡ ወእምድኅረዝ : ይትበሀል : ለቅ ዱሳን : ከመ : ይኅሥሡ : በሰማይ : ኅቡዓተ : ጽድቅ : ክፍለ : ሃይማኖት ፡

ከዚህ : በኋላ ፤ የሃይማኖት : ዕድል : የሚሆን : እውነተኛ : የተሠወረ : ምሥጢርን : በሰ ማይ : ይፈልጉ : ዘንድ : በእኔ : ቃል : ለቅዱሳን : በመጻሕፍት : ይነገራል ፡

፴፮ ፡ እስመ : ሠረቀ : ከመ : ፀሐይ : ዲበ : የብስ ፡

ዕውቀት : እንደ : ፀሐይ : ወጣ ልና ፡

ወጽልመት : ኀለፈ ፡

ድንቊርና አልፏልና ፡

ወብርሃን : ዘኢይትኌለቍ : ይከውን ፡

ስፍር : ቍጥር : የሌለው : ዕውቀት : ይሰጣል ፡

፴፯ ፤ ወበጕልቈ ፡ መዋዕል ፡ ኢይበውኡ ፤
ጻድቃን ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ ዘመን ፡ ይኖራሉ ፡ ተብለው ፡ ወደ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ አይገቡም ፤
እስመ ፡ ቀዳሚ ፡ ተኀጕለ ፡ ጽልመት ፤
አስቀድሞ ፡ ድንቊርና ፡ ጠፍቷልና ፤

፴፰ ፤ ወብርሃን ፡ ይጸንዕ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ መናፍስት ፤
ዕውቀት ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ ጸንቷልና ፤
ወብርሃነ ፡ ርትዕ ፡ ትጸንዕ ፡ ለዓለም ፡ በቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤
በርትዓተ ፡ ሕሊና የምትገኝ ፡ ብርሃነ ፡ ጸጋ ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ፊት ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ጸንታ ፡ ትኖራለች ፤

፴፱ ፤ ወበእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ርእያ ፡ አዕይንትየ ፡ ኅቡዓተ ፡ መባርቅት ፤
በእነዚያም ፡ ወራት ፡ ዓይኖቼ ፡ የመባርቅትን ፡ ምሥጢር ፤
ወብርሃናተ ፤
ፀሐይ ፡ ጨረቃን ፡ አዩ ፤
ወኵነኔሆሙ ፤
መቻያነታቸውን ፡ አዩ ፤

፵ ፤ ወይበርቁ ፡ ለበረከት ፡ ወለመርገም ፤ በከመ ፡ ፈቀደ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤
የመላእክት ፡ ጌታ ፤ እንደወደደ ለበረከት ፡ ለመርገም ፡ ይበራሉ ፡ ይሰማሉ ፤

፵፩ ፤ ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ ኅቡዓተ ፡ ነጐድጓድ ፤
በዚያ ፡ ቦታ ፡ የነጐድጓድን ፡ ምሥጢር ፡ ሰማሁ ፤
ወሶበ ፡ ይደቅቅ ፡ በመልዕልተ ፡ ሰማይ ፤ ወቃሎሙ ፡ ይሰማዕ ፤
ይደምጽ ፡ ያበርህ ፡ ሲል ፡ ነው ፤
በዚያም ፡ ቦታ ፡ በሰማይ ፡ ላይም ፡ ብልጭ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ የመብረቅና ፡ የነጐድጓድ ፡ ቃላቸው ፡ ይሰማል ፤

፵፪ ፤ ወማኅደራተ ፡ የብስ ፡ አስተርአየኒ ፤
ይህን ፡ ዓለም ፡ አሳየኝ ፤

፵፫ ፤ ወቃል ፡ ዘነጐድጓድ ፡ ለሰላም ፡ ወለበረከት ፤
የነጐድጓድ ፡ ድምጽ ፡ ለፍቅር ፡ ለበረከት ፡ ይሰማል ፤
ወለእመ ፡ ለረጊም ፡ በቃለ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤
ለመርገምም ፡ ቢሆን ፡ በእግዚአ መናፍስት ፡ በመላእክት ፡ ጌታ ፡ ቃል ነው ፤

፵፬ ፤ ወእምድኅረዝ ፡ ተርእየኒ ፡ ሊተ ፡ ኵሉ ፡ ኅቡዓቲሆሙ ፡ ለብርሃናት ፡ ወለመባርቅት ፤
ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የፀሐይ ፡ የጨረቃና ፡ የመባርቅት ፡ ምሥጢር ፡ ተገለጸልኝ ።

፵፭ ፤ ለበረከት ፡ ወለጽጋብ ፡ ይበርቁ ፤
ለጥጋብና ፡ ለበረከት ፡ ሊሆኑ ፡ ያበራሉ ፡ ይሰማሉ ፤ መብረቅ ፡ ሲሰማ ፡ ያድጋል ፡ ያፈራልና ።

## ምዕራፍ ፲፮
## ጉባኤ

፩ ፡ በዓመት ፡ ፭፻ ፡ ወበወርኀ ፡ ሳብዕ ፡ እምዐሡሩ ፡ ወረቡዑ ፡ ለወርኃ ፡ በሕይወቶ ፡ ኄኖክ፡
እምሕይወተ ፡ ሄኖክ ፡ ሲል ፡ ነው ፡
የዚህን ፡ ዓለም ፡ አነዋወር ፡ ትቶ ፡ በገነት ፡ በኖረ ፡ ባ፭፻ ፡ ዘመን ፡ በ፯ኛው ፡ ወር ፡ በጥቅምት ፡ ጥቅምት ፡ በባተ ፡ በ፲፬ኛው ፡ ቀን፡
በውእቱ ፡ እምሳል ፡ ርኢኩ ፡
ሄኖክ ፡ ባየው ፡ ራእይ ፡ እምሳል ፡ አየሁ ፡ እሰ ፡ ኖኅ ፡ የማየ ፡ አይኅ ፡ ነገር ፡ ተገልጸለት ፡ ተናግሯል ፡
ወበይእቲ ፡ ዕለት ፡ አውሥአ ፡ ቅዱስ ሚካኤል ፡
ወይቤሎ ፡ ለቅዱስ ፡ ሩፋኤል ፡ እስ ኪል ፡ ድረስ ፡ ኖኅ ፡ ተገልጸለት ፡ ተናግሯል ፡ በሄኖክ ፡ መካከል ፡ እንደ ፡ ሹልዳ ፡ አግብቶ ፡ ተናግ ሯል ፡
ከመ ፡ ታድለቀልቅ ፡ ለማየ ፡ ለማያት ድልቅልቀ ፡ ዓቢየ ፡
ከጠፈር ፡ በላይ ፡ ያለ ፡ ሐኖስ ፡ መነዋወጥን ፡ ፈጽሞ ፡ ሲነዋወጥ ፡ አየሁ ፡ ፈጽሞ ፡ እርግፍግፍ ፡ ሲል ፡ አየሁ ፡
ወኃይሉ ፡ ለልዑል ፡
የልዑል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ኃይሉ ፡ ሊቃነ ፡ መላእክት ፡

፪ ፡ ወመላእክት ፡ አእላፈ ፡ አእላፋት ወትእልፊተ ፡ ትእልፊት ፡
ብዙ ፡ የብዙ ፡ ብዙ የሚሆኑ ፡ መላእክት ፡ ሠራዊተ ፡ መላእክት ፡
ተሀውኩ ፡ ዓቢየ ፡ ሁከተ ፡
ፈጽመው ፡ ታወኩ ፡ የሰው ፡ ጥፋት ፡ የሰው ፡ ጉዳት ፡ የማያሳ ዝነው ፡ የለምና ፡
፫ ፡ ወሰቤሃ ፡ ርኢኩ ፡ ርእሰ ፡ መዋ ዕል ፡ ዲበ ፡ መንበረ ፡ ስብሐቲሁ ፡ ይነብር ፡
ያን ፡ ጊዜም ፡ ዕለተ ፡ እሑድ ፡ ገን ዘቡ ፡ የሆነች ፡ ጌታን ፡ በጌትነቱ፡ ዙፋን ፡ ተቀምጦ ፡ አየሁት ፡
፬ ፡ ወመላእክት ፡ ወጻድቃን ፡ ዓውዶ ፡ ይቀውሙ ፡
ሊቃነ ፡ መላእክት ፡ ሠራዊተ ፡ መላእክት ፡ ከበው ፡ በዙሪያው ፡ ይቆማሉ ፡
ወሊተኒ ፡ ዓቢይ ፡ ረዓድ ፡ ነሥአኒ ፡
ጽኑ ፡ እንቅጥቅጥታ ፡ ያዘኝ ፡
፭ ፡ ወፍርሀት ፡ አኀዘኒ ፡
ፍርሃትም ፡ ያዘኝ ፡
ወሐቌየ ፡ ተቀጽዐ ፡
ወገቤ ፡ ጐበጠ ፡
ወተፈትሐ ፡
ተለያየ ፡
ወኵልያትየ ፡ ተመስወ ፡

ልቡናየ ፡ እንደ ፡ ሰም ፡ ቀለጠ፤
ኵለንታዬ ፡ ቢል ፡ ሁለንተናዬ ፡ እንደ ፡ ሰም ፡ ቀለጠ ፡ ተበተነ ፤
ወወደቁ ፡ በገጽየ፤
በግምባሬ ፡ ፍግም ፡ ብዬ ፡ ወደ ቅሁ፤

፮ ፤ ወፈነወ ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ካልአ ፡ መልአከ ፡ ቅዱሰ ፡ ፩ደ እመላእክት ፡ ቅዱሳን ፡ ወአንሥአኒ ፤
ቅዱስ ፡ ሚካኤልም ፡ ከክበሩ ፡ መላእክት ፡ አንዱን ፡ ሌላ ፡ መልአክ ፡ ልኮ ፡ አነሣኝ ፤

፯ ፤ ወሶበ ፡ አንሥአኒ ፡ መንፈስየ ፡ ገብአት ፡ እስመ ፡ ኢክህልኩ ፡ ተዐግሦ ፡ እምርእየ ፡ ዝኩ ፡ ኃይል ፤
ይህን ፡ ምሥጢር ፡ ከማየት ፡ መታገሥ ፡ አልቻልሁምና ፤ መን ፈስየ ፡ ገብዐት ፤ አእምሮዬ ፡ ተመ ለሰች ፤ አንድም ፡ አልታገሥሁ ምና ፡ ወደቁ ፡ በገጽየ ፡ ላለው፤
ወኪያሁ ፡ ሀውከ ፡ ወአንቀልቀሎ ፡ ሰማይ ፤

ወውእቱ ፡ ሀውከ ፡ ሲል ፡ ነው፤ በኪያሆን ፡ መዋዕል ፡ ሰምዐት ፡ ዮዲት[፩] ፡ እንዲል ፣ እምራእየ ፡ ውእቱ ፡ እንደ ፡ ማለት ፣ ይህን ንም ፡ ከማየት ፡ የተነሣ ፤ አንድም ፡ እምርእይ ፡ ዘንተ ፡ ወኪያሁ ፡ ሐወከ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ትርጓ ሜው ፡ አይለወጥም ፤ ወአንቀል ቀሎ ፤ ሰማይ ፡ ከመነዋወጡ ፡ የተነሣ ፤

፩ ፣ ዮዲ. ፰ ፥ ፩

፰ ፤ ወይቤለኒ ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ በእንተ ፡ ምንት ፡ ራእይ ፡ ዘከመዝ ፡ ተሀወከ ፤
ቅዱስ ፡ ሚካኤልም ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ እንዲህ ፡ የታወክህ ፡ ምን፡ ራእይ ፡ ስላየህ ፡ ነው ? አለኝ፤

፱ ፤ እስከ ፡ ዮም ፡ ሀለወት ፡ ዕለተ ፡ ምሕረቱ ፡ ወሀሎ ፡ መሐሪ ፡ ወርኁቀ ፡ መዓት ፡ ላዕለ ፡ እለ ፡ የሐድሩ ፡ ዲበ፡ የብስ ፤
ከመዓት ፡ የራቀ ፡ መሐሪ ፡ እግዚአብሔር ፡ በምሕረት ፡ አለ፤ ትች ፡ ነው ፣ ምሕረቱን ፡ የሚያ ደርግባት ፡ ቀን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እንጂ ፡ አለች ፣ ምጽዓት ፡ የደረሰ ፡ መስሎሃል?

፲ ፤ ወሶበ ፡ ትመጽእ ፡ ዕለተ ፡ ኃይል ፤
ይህን፡ ዓለም ፡ የሚያሳልፍበት ቀን ፡በደረሰ ፡ ጊዜ ፤
ወመቅሠፍት ፤
በኃጥአን ፡ የሚፈድርበት፡ ቀን፣
ወዘኮነኔ፡ እንተ፡ አስተዳለወ፡ እግዚአ፡ መናፍስት ፡ ለእለ፡ ይሰግዱ፡ ለኵነኔ፡ ጽድቅ ፤ ወለእለ ፡ ይክህዱ ፡ ለኵነኔ ፡ ጽድቅ ፤
ለእለ፡ ይሰግዱ ፡ ወለእለ ፡ ኢይ ሰግዱ ፡ ለኵነኔ ፡ ጽድቅ፡ ሲል፡ ነው ፤ ለእውነተኛ፡ ሕግ ፡ ለሚሰ ግዱ ፣ ለማይሰግዱ ፣ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ያዘጋጃት ፡ ፍርዱን፡ በሚፈርድባት ፡ ቀን ፣

ወለእለ ፡ ያነሥኡ ፡ ስሞ ፡ በከ ፤
ስሙን ፡ በከንቱ ፡ በሚያነሱ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ያዘጋጃት ፡ ፍርዱን ፡ በሚፈርድባት ፡ ቀን ፤

፮ ፤ ወተደለወት ፡ ይእቲ ፡ ዕለት ፡ ለኅሩያን ፡ መሐላ ፤
ያችም ፡ ቀን ፡ ለደናግል ፡ ተስፋ ፤

ወለኃጥአን ፡ ሐተታ ፤
ለኃጥአን ፡ ምርመራ ፡ ልትሆን ተዘጋጀች ፤

፯ ፤ ወይትከፈሉ ፡ ዒይእቲ ፡ ዕለት ፡ ፪ቱ ፡ አናብርት ፤
ብሔሞትና ፡ ሌዋታን ፡ ከደመ፡ ነፍሳቸው ፡ ይለያሉ ፤ ይህስ ፡ ተለይተው ፡ እንጂ ፡ አንድ ፡ሰዓት ፡ የሚቆዩበት ፡ ቢኖር ፡ ነው ፡ ብሎ፡ ያን፡ ጊዜ ፡ ያልፋሉ ፤

አንበሪ ፡ አንስትያዊት ፡ ዘስማ ፡ ሌዋታን ፡ ከመ ፡ ትኅድር ፡ ውስተ ፡ ልጕተ ፡ ባሕር ፡ መልዕልተ ፡ አንቅዕተ ፡ ማያት ፤
ከውኃው ፡ በላይ ፡ ባለ ፡ ጕድጓድ ፡ ትኖር ፡ ዘንድ ፡ የተፈጠረች ፡ ስሟ ፡ ሌዋታን ፡ የምትባል ፡ አንስትያዊት ፡ አንበሪ ፤

፰ ፤ ወለተባዕታይ ፡ ስሙ ፡ ብሔሞት ፡ ዘይእኅዝ ፡ በእንግድዓሁ ፡ በበድው ፡ ዘኢያስተርኢ ፤
በድወ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ በርቀት፤ አንድም ፡ ተኝቶበት ፡ የማይታየውን ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ በደረቱ ፡ የያዘው ፡ የወንዱ ፡ ስሙ ፡ ብሔሞት ፡ ይባላል ፤ ትች ፡ ነው ፤ አንስትያዊት ፡ አንበሪ ፤

፱ ፤ ወስሙ ፡ ዱንዳይን ፤
በድው ፡ ያለውን ፡ ነው ፤ ስሙም ፡ ዱንዳይን ፡ የሚባል ፤

በምሥራቀ ፡ ገነት ፤
ገነት ፡ ባለችበት ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ያለ ፡ አለው፤

በኀበ ፡ ይነብሩ ፡ ኅሩያን ፡ ወጻድቃን ፡ በኀበ ፡ ተመጠወ ፡ እምሔውየ ፤
ገነትን ፡ አያቴ ፡ ጸጋ ፡ ክብር ፡ የተቀበለባት ፤ ደናግል ፡ ሕጋውያን ፡ የሚኖሩባት ፡ገነት፡ ባለችበት ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ያለ ፡ ምድረ ፡ በዳውን ፡ የያዘ ፡ ስሙም ፡ ብሔሞት ፡ ይባላል ፤ አንስትያዊት ፡ አንበሪ ፤

ዘውእቱ ፡ ሳብዕ ፡ እምአዳም ፡
ከአዳም ፡ሰባተኛ ፡ የሆነ ፡ አዳም ፤ ሴት ፤ ሔኖስ ፤ ቃይናን ፤ መላልኤል ፤ ያሬድ ፤ ሄኖክ ፤

ቀዳሚሆሙ ፡ ለሰብእ ፡ ዘገብረ ፡ እግዚእ ፡ መናፍስት ፤
እግዚአ ፡ መናፍስት ፡ (የመላእክት፡ ጌታ) ፡ ከፈጠራቸው ፡ ሰዎች ፡ የሚቀድም ፡ ብሎ ፡ ለአዳም ፡ ቀጸለ ፤ አንድም ፡ የሚበልጥ ፡ ብሎ ፡ ለሄኖክ ፡ ቀጸለ ፤ ወንዱ ብሔሞት ፡ ይባላል ፤ አንስትያዊት ፡ አንበሪ ፤

፲ ፤ ወተሰእልክዎ ፡ ለዝኩ ፡ ካልዕ ፡ መልአክ ፡ ከመ ፡ ያርእየኒ ፡ ኃይሎሙ ፡ ለእልክቱ ፡ አናብርት ፤
የእነዚህን ፡ አውሬዎች ፡ ግብራቸውን ፡ አነዋወራቸውን ፡ ያሳየኝ፡

ዘንድ ፤ ያንን ፡ ሁለተኛውን ፡ መልአክ ፡ ጠየቅሁት ፤
እፎ ፡ ተሌለዩ ፡ በአሐቲ ፡ ዕለት ወተወድዩ ፡ ፩ዱ ፡ በልጐተ ፡ ባሕር ፡ ወ፩ ፡ በየብስ ፡ በድው ፤
በአንዲት ፡ ቀን ፡ ሁለቱ ፡ ተፈ ጥረው ፡ ተለያይተው ፡ አንዱ ፡ በየብስ ፡ አንዱ ፡ ከውኃው ፡ ላይ ፡ ባለ ፡ ጕድጓድ ፡ ሲኖሩ ፡ ምን ፡ ተመግበው ፡ ይኖራሉ ?
ብዬ ፡ ጠየቅሁት ፤ እንደ ፡ ጠየቀው ፡ በዚህ ፡ ይታወቃል ፤
፲፯ ፤ ወይቤለኒ ፡ አንተ ፡ ወልደ ፡ ሰብእ ፡ በዝየ ፡ ትፈቅድ ፡ ታእምር ፡ ዘኅቡዕ ፤
በዝየ ፡ በቦታው ፤ አንድም ፡ በነገሩ ፡ አንተ ፡ የባለ ፡ አእምሮ ፡ ልጅ ፡ የተሰወረውን ፡ ነገር ፡ በዚህ ፡ ልታውቅ ፡ ትወዳለህ ? አለኝ ፤
፲፯ ፤ ወይቤለኒ ፡ ካልዕ ፡ መልአክ ፡ ዘየሐውር ፡ ምስሌየ ፡ ወዘበኀቡእ ፡ ዘአርአየኒ ፤
ከእኔ ፡ ጋራ ፡ የሚኖር ፡ ሌላ ፡ መልአክ ፡ የተሰወረውን ፡ ምሥ ጢር ፡ አሳየኝ ፤
ዘቀዳሚ ፡ ወዘደኃሪ ፤
የፊቱንም ፡ የኋላውንም ፡ የሚያ ሳየኝ ፤
በሰማይ ፤ በውስተ ፡ ላዕሉ ፤ ወበ ውስተ ፡ የብስ ፡ በማዕምቅ ፤ ወበ አጽናፈ ፡ ሰማይ ፡ ወበመሠረተ ፡ ሰማይ ፤

ከምድር ፡ በላይ ፡ ባለ ፡ በሰማይ፤ ከሰማይ ፤ በታች ፡ ባለ ፡ በምድር፤ በጽንፈ ፡ ሰማይ ፤ በመሠረተ ፡ ሰማይ ፡ ያለውን ፡ ያሳየኝ ፡ መልአክ ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፤
ወበመዛግብተ ፡ ነፋሳት ፤
ነፋሳት ፡ ተመጥነው ፤ ተመጥ ነው ፡ እንዲነፍሱ ፡ ያሳየኝ ፤
፲፰ ፤ ወእፎ ፡ ይትከፈሉ ፡ መና ፍስት ፤
ነፋሳት ፡ ተመጥነው ፡ ተመጥነው እንዲነፍሱ ፤
ወእፎ ፡ ይትኌለቁ ፡ አንቅዕት ፤
ምንጮችም ፡ ተመጥነው ፡ ተመ ጥነው ፡ እንዲፈስሱ ፡ ያሳየኝ ፤
ወነፋሳት ፡ በኃይለ ፡ መንፈስ ፤
ነፋሳት ፡ በመልአኩ ፡ ኃይል ፡ ተመጥነው ፡ ተመጥነው ፡ እንዲ ነፍሱ ፡ ያሳየኝ ፤
ወኃይሎሙ ፡ ለብርሃነ ፡ ወርኅ ፡ የጨረቃ ፡ ብርሃን ፡ ተመጥኖ ፡ ተመጥኖ ፡ እንዲያበራ ፡ በምሥ ጢር ፡ ያሳየኝ ፤ ኃይሎሙ ፡ አለ ፡ የምሉ ፤ የሕፀፅ ፡ ብርሃን ፡ አለና፤ ብርሃን ፡ አለ ፤ የሁሉ ፡ አንድ ፡ ነውና ፤
ወከመ ፡ ኃይለ ፡ ጽድቅ ፤
ዋዊው ፡ ቀሪ ፡ ነው ፤ እውነተኛ ብርሃን ፡ እንደ ፡ መሆኑ ፡ የጨ ረቃን ፡ ብርሃን ፡ ተመጥኖ ፡ ተመ ጥኖ ፡ እንዲያበራ ፡ በምሥጢር ፡ ያሳየኝ ፤
ወከፍላተ ፡ከዋክብት ፡ በበስሞሙ ፤

የከዋክብትን ፡ አከፋፈል ፡ በየስ ማቸው ፡ ያሳየኝ ፡ መልአክ ፡ እንዲህ ፡ አለኝ፤

፲፱ ፤ ወዅሉ ፡ ክፍል ፡ ይትከፈል ፤

ለሁሉ ፡ መጠን ፡ አለው ፡

ወነጐድጓድ ፡ በሙዳቃቲሆሙ ፣

መብረቅ ፡ ነጐድጓድ ፡ በሚሰሙ በት ፡ ጊዜ ፡ ለነጐድጓድ ፡ መጠን ፡ አለው ፤

ወለዅሉ ፡ ክፍል ፡ ዘይትከፈል ፤

ለአሸዋው ፣ ለድኙ ፡ መጠን ፡ አለው ፤

፳ ፤ ወመብረቅ ፡ ከመ ፡ ይበርቅ ፣

መብረቅ ፡ ከመ ፡ ይብርቅ ፡ ሲል ፡ ነው ፤

መብረቅ ፡ ይሰማ ፡ ዘንድ ፣

ወትዕይንቶሙ ፡ ከመ ፡ ፍጡነ ፡ ይስ ምዑ ፤

የሰዎች ፡ ሠራዊት ፡ ፈጥነው ፡ ይሰሙ ፡ ዘንድ ፤ እንድም ፡ ይስ ምዑ ፡ ቢል ፡ የድኝና ፡ የአሸዋ ፡ ሠራዊት ፡ መብረቅ ፡ ነጐድጓድ ፡ ይሰሙ ፤

እስመ ፡ ቦቱ ፡ ለነጐድጓድ ፡ ምዕራ ፋት ፤

በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ለነጐድጓድ ፡ ማረፊያ ፡ አለውና ፤

በትዕግሥት ፡ ለቃለ ፡ ዚአሁ ፡ ተው ህበ ፤

ታግሦ ፡ ታግሦ ፡ ሊሰማ ፡ ለድ ምፁ ፡ መሰማት ፡ ተሰጠው፤

፳፩ ፤ ወኢይትሌለዩ ፡ ኢነጐድጓድ፤ ወኢመብረቅ ፤

ይህ ፡ የመብረቅ ፣ ይህ ፡ የነጐ ድጓድ ፡ ድምጽ ፡ ነው ፡ ተብሎ ፡ አይለዩም፤

ወኢ፩ዱ ፡ እሐዱ ፤

አንዱ ፡ ስንኳ ፡ ከአንዱ ፡ አይለ ዩም ፤

በመንፈስ ፡ ፪ሆሙ የሐውሩ፤

በመልአኩ ፣ በነፋስ ፡ ምግብና ፡ ይመገባሉ ፣ ይሔዳሉ ፤

፳፪ ፤ ወኢይትሌለዩ ፤

ይህ ፡ የመብረቅ ፡ የነጐድጓድ ፡ ድምጽ ፡ ነው ፡ ተብሎ ፡ አይለ ዩም ፤

እስመ ፡ ሶበ ፡ ይበርቅ ፡ መብረቅ ነጐድጓድ ፡ ቃሎ ፡ ይሁብ ፤

መብረቅ ፡ በማ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ነጐ ድጓድ ፡ ቃሉን ፡ ያሰማልና፣ ወኢይ ትሌለዩ ፡ ላለው ፤

ወመንፈስ ፡ በጊዜሃ ፡ የዐርፍ ፤

መብረቅን ፣ ነጐድጓድን ፡ የሚመ ግብ ፡ ነፋስ ፡ በጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ያርፋል ፤

፳፫ ፤ ወዕሩየ ፡ ይከፍል ፡ በማእከ ሎሙ ፤

ይህ ፡ ነፋሱ ፡ በአሸዋውና ፡ በድኙ፡ መካከል ፡ አስተካክሎ ፡ ይከፍ ላል ፤

እስመ ፡ መዝገበ ፡ ጊዜያቲሆሙ ዘኖባ ፡ ውእቱ ፣

መብረቅና ፡ ነጐድጓድ ፡ በጊዜያ ቸው፡ ጊዜ ፡ የሚያርፉበት ፡ የአ ሸዋ ፡ ወገን ፡ ድኝ ፤ የድኙ ፡ ወገን ፡ አሸዋ ፡ ነውና ፡ አስተ ካክሎ ፡ ይከፍላል ፤

፷፬ ፡ ወዕዱ ፡ ዕዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ በጊዜሁ ፡ በልጓም ፡ ይትአኀዙ ፡
ከመብረቅና ፡ ከነጐድጓድ ፡ አን ዱም ፡ አንዱም ፡ በሥልጣን ፡ ይገታሉ ፡
፷፭ ፡ ወይትመየጡ ፡ በኃይለ ፡ መንፈስ ፡
በነፋሱ ፡ በመልአኩ ፡ ኃይል ፡ ይተጋሉ ፡
ወይትነዳዕ ፡ ከመዝ ፡ በከመ ፡ ብዝኃ አድዋለ ፡ ምድር ፡
እንደ፡ ምድር ፡እውራጃ፡ ብዛት፡ መጠን ፡ ብርሃኑ ፡ ይነዛል ፡
፷፮ ፡ ወመንፈስ ፡ ባሕር ፡ ተባዕታይ ፡ ውእቱ ፡
ባሕሩን ፡ የሚከፍል ፡ ነፋስ ፡ ኃያል ፡ነው ፡ጽኑ ፡ ነው ፡
ወበከመ ፡ ኃይለ ፡ ጽንእታ ፡ በልጓም ያገብአ ፡
እንደ ፡ ጽንዓቷ ፡ ኃይል ፡ በልጓም፡ (በሥል ጣን) ፡ ይመል ሳታል ፡
፷፯ ፡ ወከመዝ ፡ ትትነዳዕ ፡ ወት ዘራዕ ፡ በኵሉ ፡ አድባረ ፡ ምድር፡
በምድሩ፡ ተራራ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ዚህ፡ ትነዛለች ፡ ትዘራለች ፡
፷፰ ፡ ወመንፈስ ፡ አስሐትያ ፡ መል አክ ፡ ዚአሁ ፡ ውእቱ ፡
ውርጭን ፡ የሚያመጣ ፡ ነፋስ ፡ ባልደረባው ፡ መልአክ ፡ ነው ፡
ወመንፈስ ፡ በረድ ፡ መልአክ ፡ ኄር ፡ ውእቱ ፡
በረድን ፡ የሚያመጣው ፡ መልአክ፡ ቸር ፡ ነው ፡

፷፱ ፡ ወመልአከ ፡ ሐመዳ ፡ ኀደገ ፡ በእንተ ፡ እከየ ፡ ዚአሁ ፡
ስለጽናቱ ፡ ኃይል ፡ ዋግን ፡ የሚ ያመጣ፡ ነፋስ ፡ አንድም ፡ መልአክ፡ ፈጥኖ ፡ ፈጥኖ ፡ ማምጣትን ፡ ተወ ፡
ወመንፈስ ፡ ቦቱ ፡ ለባሕቲቱ ፡
ለብቻው ፡ ባልደረባ ፡ አለው ፡
፸ ፡ ወዘየዐርግ ፡ እምኔሁ ፡ ከመ ፡ ጢስ ፡ ውእቱ ፡
ከእርሱ ፡ የሚወጣው ፡ እንደ ፡ ጢስ ፡ ያለ ፡ ነው ፡
ወስሙ ፡ ደደክ ፡
ስሙም ፡ ቀቅ ፡ ይባላል ፡
፸፩ ፡ ወመንፈስ ፡ ጊሜ ፡ ኢይት ኀበር ፡ ምስሌሆሙ ፡ ውስተ ፡ መዛ ግብቲሆሙ ፡
ጉምን ፡ የሚመግብ ፡ ነፋስ ፡ አንድም ፡ መልአክ ፡ ከሐመድ (ከዋግ) ፡ ከውርጭ፡ ጋራ ፡ በቦታ፡ አይተባበርም ፡
እላ ፡ መዝገብ ፡ ቦቱ ፡ ለባሕቲቱ ፡
ለብቻው ፡ ቦታ ፡ አለው ፡ እንጂ፡
እስመ ፡ ምሕዋረ ፡ ዚአሁ ፡ በስብሐት ፡ ወበብርሃን ፡ ወበጽልመት በክረምት ፡ ወበሐጋይ ፡
ምግብናው ፡ በብርሃን ፡ በጨለማ ፡ በክረምት ፡ በበጋ ፡ ነውና ፡
፸፪ ፡ ወመዝገበ ፡ ዚአሃ ፡ ብርሃን ፡ ውእቱ ፡
ቦታዋ ፡ ብሩህ ፡ ነው ፡
ወመልአካ ፡ ውእቱ ፡
ባልደረባዋ ፡ መልአክ ፡ ነው ፡

ወመንፈሰ ፡ ጠል ፡ ማኅደሩ፡ በአጽናፈ፡ ሰማይ ፡ ሙፃኡ ፤
ጠልን ፡ የሚያመጣ ፤ የሚመ ግብ ፡ የነፋስ ፡ መልእክ ፡ ማደ ሪያው ፡ መውጫው ፡ በጽንፈ ፡ ሰማይ ፡ ነው ፤
፴፫ ፤ ወድሩግ ውእቱ ፡ ምስለ ፡ መዛግብተ ፡ ዝናም ፤
ዝናምን ፡ ከሚያመጣ ፡ ነፋስ ፡ በታ፡ ጋራ ፡ ጠልን ፡ የሚያመጣ ነፋስ ፡ በታ ፡ አንድ ፡ ነው ፤
ወምሕዋረ ፡ ዚአሁ ፡ በክረምቱ ፡ ወበሐጋይ ፤
ምግብናውም ፡ በክረምት ፡ በበጋ ፡ ነው ፤
፴፬ ፤ ወደመና ፡ ዚአሁ ፤
የጠል ፡ ደመና ፤
ወደመና ፡ ጊሜ ፡ ኅቡር ፤
ወፈውሰ ፡ ኵሉ ፡ ፍጡነ ፡ ጊሜ[፩] ፡ እንዲል ፤ የዝናሙ ፡ ደመና ፤ ኅቡር ፤ አንድ ፡ ነው ፤
ወ፩ዱ ፡ ለካልኡ ፡ ይሁብ ፤
ዝናም ፡ መግቦ ፡ ለጠል ፤ ጠል ፡ መግቦ ፡ ለዝናም ፡ ይሰጣል ፤
፴፭ ፤ ወመንፈሱ ፡ ለዝናም ፡ ሶበ ፡ ይትሐወክ ፡ እምነ ፡ መዝገበ ፡ ዚአሁ ይመጽኡ ፡ መላእክት ፡ ወያርኅዉ ፡ መዝገበ ወያወጽእዎ ፤
ዝናምን ፡ የያዘ ፡ ነፋስ ፡ በተነ ዋወጠ፡ ጊዜ ፤ መላእክት፡ መጥ ተው ፤ መስኮቱን ፡ ከፍተው ፡ ያወጡታል ፤ መነዋወጡ ፡ አው ጡኝ፡ አውጡኝ ፡ ሲል፡ ነውና፤

[፩] ፤ ሲራ. ፵፫ ፥ ፳፬

፴፮ ፤ ወሶበ ፡ ይዘሬዕ ፡ ዲበ ፡ ኵሉ ፡ የብስ ፡ ይትኀበር ፡ ዲበ፡ ኵሉ ፡ ማይ ፡ ዘዲበ ፡ የብስ ፤
በዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ በተነዛ ፡ ጊዜ ፤ በዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ ካለው ፡ ውሀ፡ ጋራ ፡ የዝናሙ ፡ ውሀ ፡ በተባበረ፡ ጊዜ ፤
፴፯ ፤ ወሶበ ፡ ይትኀበር ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ፡ ምስለ ፡ ማይ ፤ ዘዲበ ፡ የብስ ፤ በዓለሙ ፡ ካለው ፡ ውሀ ፡ ጋራ ፡ የዝናሙ ፡ ውሀ ፡ በተባበረ ፤ ጊዜ ፤
እስመ ፡ ኮኑ ፡ ማያት ፡ ለእለ ፡ የኀድሩ ዲበ ፡ የብስ ፤
እስመ ፡ ቀሪ ፡ ነው ፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ላሉ ፡ ሰዎች ፡ ምግብ፡ ይሆናሉ ፤
እስመ ፡ ሲሳያ ፡ ለየብስ ፡ እምነበ ፡ ልዑል ፡ ዘእምሰማይ ፡ ውእቱ ፤
የዚህ ፡ ዓለም ፡ ምግብ ፡ ከል ዑል፡ ከእግዚአብሔር ፡ ታዝዞ ፤ ከሰማይ ፡ የወረደው ፡ ነውና ፤
እስመ ፡ በእንተዝ ፡ መስፈርት ቦቱ ፡ ለዝናም ፤
እስመ ፡ ቀሪ ፡ ነው ፤ ዝናም ፡ ለሰው ፡ ምግብ ፡ ስለሆነ ፡ ተመ ጥኖ ፡ ይወርድ ፡ ዘንድ ፡ መመ ጠን ፡ አለው ፤
ወመላእክት ፡ ይትሜጠውዎ ፤
መላእክት ፡ ይቀበሉታል ፤ ይመ ግቡታል ፤

፴፰ ፤ እሉንተ ፡ ኵሉሙ ፡ ርኢኩ ፡ እስከ ፡ ገነተ ፡ ጻድቃን ፤

ጻድቃን ፡ እስካሉበት ፡ ገነት ፡ ድረስ ፡ ደርሼ ፡ እነዚህን ፡ ሁሉ ፡ አየሁ ፤ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ትች ፡ ነው ፤ እን ዲህ ፡ እንዲህ ፡ አየሁ ፤ ብሔሞ ትና ፡ ሌዋታን ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ተፈጥረው ፡ አንዱ ፡ በየብስ ፣ አንዱ ፡ ከባሕሩ ፡ በላይ ፡ ባለ ፡ በዋሻ ፡ ሲኖሩ ፡ ምን ፡ ተመግበው ፡ ይኖ ራሉ ? ብዬ ፡ ጠየቅሁት ፤

፴፱ ፤ ወይቤለኒ ፡ መልአከ ፡ ሰላም ፡ ዘምስሌየ ፡ ይሄሉ ፤

ይቤለኒና ፡ ይቤለኒ ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ከእኔ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋራ ፡ ፍቅር ፡ አንድነት ፡ ያለው ፡ ባልደረባዬ ፡ መልአክ ፡ እንዲህ ፡ አለኝ ፤

እሉ ፡ ክልኤቱ ፡ አናብርት ፡ ላዕለ ፡ ዕበይ ፡ ዘእግዚአብሔር ፡ ድልዋን ፡ ይሴሰዩ ፡ በከመ ፡ መቅሠፍቱ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በከ ፤

እነሆ ፡ ሁለቱ ፡ አውሬዎች ፡ የእግዚአብሔር ፡ መቅሠፍቱ ፡ ረሀብ ፡ በከ ፡ (ከንቱ) ፡ ልታ ደርጋቸው ፡ እንዳትመጣ ፡ ይመ ገቡ ፡ ዘንድ ፡ የተዘጋጁ ፡ ናቸው ፤ አንድም ፡ ድልዋነ ፡ ቢል ፡ የተ ዘጋጁ ፡ ሁነው ፤ አንድም ፡ ድልዋን ፡ ቢል ፡ ተዘጋጅተው ፡ ይመገባሉ ፡

፵ ፤ ወይትቀተሉ ፡ ደቂቅ ፡ ምስለ ፡ እማቲሆሙ ፤

እምተቀትሉ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ ሴቶች ፡ ልጆች ፡ ከናቶቻቸው ፡ ጋራ ፤

ወውሉድ ፡ ምስለ ፡ አበዊሆሙ ፤

ወንዶች ፡ ልጆችም ፡ ከአባቶቻ ቸው ፡ ጋራ ፡ እሊህን ፡ ቢያዩ ፡ በሞቱ ፡ ነበር ፤

ሶበ ፡ ተዐርፍ ፡ መቅሠፍቱ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ዲቤሆሙ ፡ ተዐርፍ ፤

የእግዚአብሔር ፡ መቅሠፍት ፡ በምትመጣበት ፡ ጊዜ ፡ በእለ ፡ ብሔ ሞት ፡ ታርፋለች ፡ ታሳልፋቸዋ ለች ፤

፵፩ ፤ ከመ ፡ ኢትምጻእ ፡ መቅሠፍቱ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ በከ ፤

ከምጽአት ፡ አስቀድሞ ፡ ዛሬ ፡ መቅሠፍቱ ፡ በከ(ከንቱ) ፡ ልታደር ጋቸው ፡ እንዳትመጣ ፤

ዲበ ፡ እሉ ፡ ድኅረ ፡ ትከውን ፡ ኵነኔ በምሕረቱ ፡ ወበትዕግሥቱ ፤

በቸርነቱ ፣ በትዕግሥቱ ፣ ኋላ ፡ ትሆናለች ፤ ኋላ ፡ ያሳልፋቸዋል ፤ በድለው ፡ ይታገሣቸዋል ፡ ማለት ፡ አይደለም ፤ በቸርነቱ ፡ አኑሮ ፡ ያሳ ልፋቸዋል ፡ ሲል ፡ ነው ፤ አንድም ፡ ድልዋን ፡ ይሴሰዩ ፡ ይመገቡ ፡ ዘንድ ፡ የተዘጋጁ ፡ ናቸው ፤ አንድም ፡ ድልዋነ ፡ ቢል ፡ የተዘጋጁ ፡ ሁነው ፡ ይመገባሉ ፤ በከመ ፡ መቅሠፍቱ ፤ እነርሱን ፡ የመገበ ፡ ይመገበ ናል ፡ በማይሉ ፡ ሰዎች ፡ እነርሱን ፡

አብነት ፡ ሳይሰጥ ፡ መቅሠፍቱ፡ በክ ፡ ሊያደጋርቸው ፡ እንዳይ መጣ ፡ ይመገቡ ፡ ዘንድ ፡ የተ ዘጋጁ ፡ ናቸው ፤ ወይትቀተሉ ፤ እነርሱን ፡ የመገበ ፡ ይመግበናል ፡ የማይሉ ፡ ሰዎች ፡ ሴቶች ፡ ልጆች፡ ከእናቶቻቸው ፡ ጋራ ፡ ወንዶች ፡ ልጆች ፡ ከአባቶቻ ቸው ፡ ጋራ ፡ ይሞታሉ ፤ሰበ ፡ ተዐርፍ ፡ መቅሠፍቱ ፤ እነርሱን ፡ የመገበ ፡ ይመግበናል ፡ በማይሉ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ መቅሠፍቱ ፡ ታድ ርባቸዋለች ፤ ታሳልፋቸዋለች ፤ ከመ ፡ ኢትምጻእ ፤ እነርሱን ፡ የመገበ ፡ ይመግበናል ፡ በማይሉ ፡ ሰዎች ፡ መቅሠፍቱ ፡ በክ ፡ ልታ ደርጋቸው ፡ እንዳትመጣ ፤ ድኅረ ፡ ትከውን ፤ እነርሱን ፡ የመገበ ፡ ይመግበናል ፡ በማይሉ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ በቸርነቱ ፡ ታግሦ ፡ ታግሦ ፡ ኋላ ፡ ታሳልፋቸዋለች::

## ምዕራፍ ፲፯

### ገባኢ

፩ ፤ ወርኢኩ ፡ በእማንቱ ፡ መዋዕል ፡ ተውህቡ ፡ ለእልክቱ ፡ መላእክት ፡ አሕባል ፡ ነዊኃን ፤

በእነዚያም ፡ ወራቶች ፡ ለእነዚያ መላእክት ፡ ረጃጅሞች ፡ ገመዶች ሲሰጡ ፡ አየሁ ፤ (ሥልጣን) ፤ አን ድም ፡ ደገኛ ፡ እእምሮ ፡ ሲሰጥ ፡ አየሁ ፤

፪ ፤ ወነሥኡ ፡ ሎሙ ፡ ክንፈ ፤ ወሠረሩ ፡ ወሖሩ ፡ መንገለ ፡ መስዕ ፤

ዕውቀትን ፡ (ሥልጣንን)፡ ተቀብ ለው ፡ ወደ ፡ መስዕ ፡ ሄዱ ፤

፫ ፤ ወተስእልክዎ ፡ ለመልአክ ፡ እንዘ ፡ እብል ፡ ለምንት ፡ ነሥኡ ፡ እሉንተ ፡ አሕባለ ፡ ነዊኃነ ፡ ወሖሩ ፤

እሊህን ፡ እእምሮታት ፡ (ረጃጅም ገመዶች፡) ለምን ፡ ተቀብለው ፡ ሄዱ ? ብዬ ፡ መልአኩን ፡ ጠየቅ ሁት ፤

፬ ፤ ወይቤለኒ ፡ መልአክ ፡ ዘም ስሌየ ፡ ሖሩ ፡ ከመ ፡ ይመጥኑ ፡ አም ጣናተ ፡ ጻድቃን ፤

ከእኔ ፡ ጋር ፡ ያለ ፡ መልአክም ፡ የጻድቃንን ፡ ቦታ ፡ ሊሠፍሩ ፡ ገመድ ፡ ተቀብለው ፡ ሄዱ ፡ አለኝ ፤ አንድም ፡ የጻድቃንን ፡ ቦታ ፡ ሊያውቁ ፡ ዕውቀትን ፡ ተቀብለው ፡ ሄዱ ፤

፭ ፤ ወይቤለኒ ፡ መልአክ ፡ ዘየሐውር ፡ ምስሌየ ፡ እሉ ፡ እሙንቱ ፡ አምጣናተ ፡ ጻድቃን ፤

ከእኔ ፡ ጋራ ፡ የሚኖር ፡ ባልደረ ባዬ ፡ መልአክም ፡ እሊህ ፡ የጻድ ቃን ፡ መለኪያዎች ፡ ናቸው ፡ አለኝ ፤

ወማዕሠረ ፡ ጻድቃን ፡ ያመጽኡ፡ ከመ ፡ ይትመርጐዙ ፡ ዲበ ፡ ስሙ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤